...ቢዎ... ...ዜ...
...ንቋነት ... ሰዎች ጽሑፎች ውስ...
...ው ይሆናል ። ይህ ግን እውነት አይደለም ፡
...ቹ የተወሰዱት አፋቸውን ባማርኛ ከፈቱ
...ጥ መሆኑን ለማስገንዘብ እንወዳለን ።

# መግቢያ

በ1962 ዓ.ም. በትምህርት መገናኛ ዘዴዎች ድርጅት ጥያቄ መሠረት ለ11ኛ ክፍል በሬዲዮ የማርኛ ትምህርት አቀርበን ነበር ። ትምህርቱን ባቀረብንበት ጊዜ ዋና ዓላማችን በተለይ የ11ኛ ክፍል በጠቅላላውም የ2ኛ ደረጃ ተማሪዎች ሲጽፉ የሚያደርጓቸውን ዋና ዋና የስሕተት ዓይነቶች ለመጠቆምና እነዚሁ ስሕተቶች የሚወገዱባቸውን መንገዶች ለማመልከት ነበር ። ኋላ ግን ፡ አብዛኞቹ ስሕተቶች በዩኒቨርሲቲ ተማሪዎች ድርሰቶችና እንዲሁም ባንዳንድ ጋዜጦችና መጻሕፍት ውስጥ እየተደጋገሙ መከሰታቸውን ስላጤን ፡ ትምህርቱን ለ2ኛ ደረጃ ተማሪዎች ብቻ ሳይሆን ጥሩ የመጻፍ ልምድ ለሌለው ለማንኛውም ሰው ሊረዳ እንደሚችል በማመን ጥቂት ሰፋ አድርገን በመጽሐፍ መልክ አቀርበነዋል ።

አንዳንዶቹ ስሕተቶች ከጥንቃቄ ጉድለት የተነሣ ሊደርሱ የሚችሉ ናቸው ። ብዙዎቹ ግን ፡ ስሕተትነታቸው ልብ ካለመደረጉ የተነሣ ባንዳንድ ጸሐፊዎች ዘንድ በጣም ተለምደው ሥር ሰደዋል ።

አንዳንድ አንባቢዎች ፡ ስሕተቶቹን ሲመለከቱ ምናልባት አማርኛን በ2ኛ ቋንቋነት ከሚናገሩ ሰዎች ጽሑፎች ውስጥ የተለቀሙ ይመስሏቸው ይሆናል ። ይህ ግን እውነት አይደለም ፡ እንዲያውም አብዛኞቹ የተወሰዱት አፋቸውን ባማርኛ ከፈቱ ሰዎች ድርሰቶች ውስጥ መሆኑን ለማስገንዘብ እንወዳለን ።

ሆኖም ለዓላማችን ተገቢ ስላልሆነ፣ የጸሐፊዎቹን ስም ለመግለጽ አልፈለግንም ።

መጽሐፏ በሁለት ዋና ዋና ክፍሎች ልትመደብ ትችላለች። የመጀመሪያው ክፍል ከምዕራፍ 1 እስከ ምዕራፍ 4 መጨረሻ ድረስ ያለው ነው ። በዚህ ክፍል ከስሕተቶቹ ጋር ቀጥታ ግንኙነት ያላቸው የሰዋስው ሕጎች ተዘርዝረዋል ።

በየምዕራፉ መጨረሻ ላይ አንባቢው እንዲያርማቸው የቀረቡ የስሕተት ምሳሌዎች ይገኛሉ ። ሁለተኛው ክፍል ከምዕራፍ አምስት ጀምሮ እስከ መጽሐፉ መጨረሻ ድረስ ያለው ገለጻ ነው ። በዚህ ክፍል የተለያዩ ምሳሌዎች በማቅረብ በጠቀላላ ስለድርሰት አጻጻፍ አንዳንድ ዘዴዎች ለማቅረብ ተሞክሯል ።

ጥሩ ድርሰት ለመጻፍ ከመምህራን የሚሰጡ ምክሮችን መረዳት ብቻ በቂ አይደለም ። አስቀድሞ የመጻፍ ፍላጎት እንዲኖር ያሻል ። ዕውቀትንም ለማዳበር ብዙ ማንበብ በጣም ያስፈልጋል።

ለመጻፍ የሚፈልግ ሰው ዓላማ ሊኖረው ይገባል ። ዓላማው አንባቢን ለማዝናናት ወይም አንድ ነገር ለማስረዳት ሊሆን ይችላል ። ለማዝናናትም ሆነ ለማስረዳት ጽሑፉ በቋንቋ ጥራትና በሐሳብ አደራደር ስልት አንባቢን የሚያስደስትና የሚማርክ መሆን አለበት ። እንዲህ ካልሆነ ለአንባቢ የማይጥም የሚያሰለች ብጤ ይሆንና ሳይነበብ ይቀራል ።

ለምሳሌ፣ ከዚህ ቀጥሎ ያለውን ካንድ ጋዜጣ የተገለበጠ ጽሑፍ እንመልከት ።

ጥንት በአሰምሮ ጥናት እየተገኘ ትሠራበት የነበረው የልምምድ ትምህርት ዛሬ በማንበብና በመጻፍ በሚገኘው የዕውቀት ደረጃ ጋር እያስተካከለች ፣ ከዘመናዊ የዕውቀት ወቅት ጋር ተባብራ ለመሥራትና በመሥራት ብዙ የጥበብ ሰዎች ያመሰግኗታል ።

ከፍ ብለን እንደ ተመለከትነው ፡ ሰውቀቶች ከሰው ልክ ብዛታቸው አያንስም ብንል አያሳፍረንም ። የዓለም አንድነት ወይም ብልጫነት በግል ኑሮው ደርጅቶ ሰላምና በቂ ማስረጃው በበኩሉ ምስክር ሆኖ ለመገኘት የሚያበቃው ፡ አገሩን በልዩ ልዩ አቀዋም ሠርቶ ሲያስመሰግናት 'ታላቋ ወይም ታላቂቷ አገር ይህች ናት' የሚል ስመ ጥሩውን ስም ከሌላው ዓለም ስመ አጠራር ይበልጥ የስም ጌጥ ያሰጣታል ።

በእንደዚህ ያለ አጻጻፍ የቀረበን ድርሰት በማንበብ ጊዜውን ለማባከን የሚፈልግ ሰው ስለማይኖር ፡ ጥቂት ማንበብ እንደ ጀመረ ጥሎት ጊዜ ወደማይጠፋበት ድርሰት ያልፋል ። ደራሲው አንድ መልእክት ለማስተላለፍ የፈለገ ቢመስልም ያጻጻፉ ድክመት አንባቢ እንዲያጣ ሊያደርገው እንደሚችል ያስተውሏል ።

እነሆ እንግዲህ ፡ ይህቺ ትንሽ መጽሐፍ በመጠኑም ቢሆን ባንባቢ ዘንድ የሚጠላውና የሚወደደው ያጻጻፍ ዓይነት የቱ የቱ እንደሆነ ለማሳየት ስለምትሞክር ፡ የመጻፍ ፍላጐት ኖሮት ልምዱ ለሌለው ለማንኛውም ሰው ልትጠቅም ትችላለች የሚል እምነት አለን ።

# ምዕራፍ አንድ

## አጭር ሰዋስዋዊ መግለጫ

ተማሪዎችም ሆኑ ሌሎች ሰዎች ሲጽፉ በይበልጥ የሚሳሳቱት ዐረፍተ ነገር በማቀናበር ረገድ ጥንቃቄ ሲጎድላቸው ነው ። ይህም ዐይነቱ ጉድለት ሰዋስዋዊ ስሕተት ይባላል። ስለዚህም በድርሰት ውስጥ ተደጋጋሚ ስሕተት የሚደረግባቸው የሰዋስው ክፍሎች በዚህ ምዕራፍ ውስጥ ባጫጭሩ ተጠቁመዋል ።

1· የስም ሞያ

ስም በዐረፍተ ነገር ውስጥ አምስት ዋና ዋና ሞያዎች አሉት ።

እነሱም ፡

1· ባለቤት

2· ቀጥተኛ ተሳቢ

3· የመስተዋደድ ተገኘ

4· መሙያ

5· ተጣማሪ ናቸው ።

ከነዚህ ውስጥ ተማሪዎች በሚጽፉበት ጊዜ በይበልጥ ስሕተት የሚያደርጉት በመጀመሪያዎቹ ሦስት የሙያ ዐይነ

ቶች ላይ ስለሆነ ፡ ሐተታችን በዚሁ ላይ ያተኩራል ።

ለምሳሌ ፡ የሚከተለውን የዐረፍተ ነገር ጉድለት እናስተውል ።

ም. 1 ወጣቶች በሚኖሩበት ኅብረተሰብ መካከል በሥራቸው ፡ ባለባበሳቸው ፡ ባነጋገራቸው በጠቅላላው ባኗኗር ዘዴያቸው ከቀድሞው ትውልድ ጋር ለመግባባት በሚያደርጉት ብርቱ ጥረት ተቀባይ በማጣታቸው ችግራቸውን እያበረከተባቸው ሔዷል ።"

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ችግራቸውን እያበረከተባቸው ሔዷል ለሚለው ሐረግ ባለቤቱ የቱ ነው ብለን ብንጠይቅ ከዐረፍተ ነገሩ ውስጥ መልስ አናገኝም ። በሌላ አባባል ችግራቸውን እያበረከተባቸው የሔደው ማነው? ወይንም ምንድነው ብንል መልስ አናገኝም ። ይህን ዐረፍተ ነገር የጻፈው ተማሪ ግን ፡ ምናልባት . . . ተቀባይ በማጣታቸው የሚለው ሐረግ ባለቤት ይሆናል ብሎ ገምቶ ይሆናል ። ነገር ግን ፡ ይህና አድርጎ ላስተዋለው ሰው ይህ ሐረግ መስተዋድድ ስለ ወደቀበት ፡ የመስተዋድድ ተገዥ እንጂ ባለቤት ሊሆን አይችልም ። ስለዚህ ይህን ዐረፍተ ነገር በቀላሉ ለማቃናት የተፈለገ እንደሆነ ፡ በማጣታቸው በሚለው ቃል ላይ የወደቀውን መስተዋድድ "በ"ን ማንሣትና ተቀባይ ማጣታቸው የሚለውን ሐረግ የዐረፍተ ነገሩ ባለቤት ማድረግ ነው ። አለበለዚያም ሌላውን ሁሉ እንዳለ ትተን ችግራቸውን እያበረከተባቸው ሔዷል የሚለውን ሐረግ ችግራቸው እያበረከተባቸው ሔዷል ብሎ በማንበብ ተሳቢ የነበረውን ባለቤት

---

ም ምሳሌ ፡

በማድረግ ዐረፍተ ነገሩን ማቅናት ይቻላል ። እንዲሁም ስናደርግ ፡ ተማሪው ቀጥተኛ ተሳቢ ያደረገውን ችግራቸውን "ን" ትቱን ባለቤት ማድረጋችን ነው ። ስለዚህ የተስተካከ ለው ዐረፍተ ነገር በሁለቱም መንገድ እንደሚከተለው ይሆናል ።

ሀ. መስተዋድዱን በማስቀረት ፡— ወጣቶች በሚኖ ሩበት ኅብረተሰብ መካከል በሥራቸው ፡ ባለባበሳ ቸው ፡ ባነጋገራቸው በጠቅላላው ባኗኗር ዘዴያ ቸው ከቀድሞው ትውልድ ጋር ለመግባባት በሚ ያደርጉት ብርቱ ጥረት ተቀባይ ማጣታቸው ፡ ችግራቸውን እያበረከተባቸው ሔዷል ።

ለ. ቀጥተኛውን ተሳቢ ወደ ባለቤትነት ለውጠ ከግሡ ጋር እንዲስማማ በማድረግ ፡ ወጣቶች በሚኖሩበት ኅብረተሰብ መካከል በሥራቸው ፡ ባለባበሳቸው ፡ ባነጋገራቸው በጠቅላላው ባኗኗር ዘዴያቸው ከቀድሞው ትውልድ ጋር ለመግባባት በሚያደርጉት ብርቱ ጥረት ተቀባይ በማጣታ ቸው ችግራቸው እየበረከተባቸው ሔዷል ።

ከዚህ በላይ ያየነው ምሳሌ የሚያብራራው ስም በሞያ ከግሡ ጋር ሳይስማማ ሲቀር ዐረፍተ ነገር እንዴት እንደሚ ዛባ ነው ።

ዐዋጅ ፡— ባማርኛ ቋንቋ ማንኛውም ዐረፍተ ነገር ባለቤትና ማሠሪያ ግሥ የግድ ሊኖረው ያስፈልጋል ። ከሁለቱ አንዱ የጐደለው ከሆነ ግን ዐረፍተ ነገር ሊሆን አይችልም ።

ከዚህ ቀጥለን ስለያንዳንዱ የስም ሞያ በዝርዝር እንነጋ ገር ።

## 1·1 ባለቤት

ባለቤት የምንለው የተጠቀሰውን ድርጊት የሚፈጽመውን ወይንም እንዲፈጸም የሚያደርገውን ቃል ወይንም ሐረግ ነው ። በሌላ አነጋገር አድራጊ ወይንም ድርጊት አስፈጻሚ ብለን ልንጠራው እንችላለን ። በተጨማሪም አንዳንድ ሁኔታ የተከሰተበት ስም ወይንም ሐረግ ባለቤት ይባላል ።

ም· 2 ከበደ መጣ ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ የመምጣትን ተግባር የፈጸመው ወይንም አድራጊው ከበደ የሚለው ስም ነው ። ስለዚህም ከበደ የግሡ የመጣ ባለቤት መሆኑ ነው ።

ም· 3 አስተዳዳሪው ሠራተኛውን አስጠራው ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ደግሞ ፡ አስተዳዳሪው የሚለው ድርጊት አስፈጻሚ በመሆኑ የግሡ ባለቤት ሆኗል ።

ም· 4 ከበደ ፣ አበበና ተፈራ ትናንት መጡ ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ሦስት ባለቤቶች አሉ ። እነሱም ከበደ ፣ አበበ ፣ ተፈራ የተባሉት ስሞች ናቸው ። በዚሁ ሁናቴ የአንድ ዐረፍተ ነገር ባለቤት መሆን የሚችለው አንድ ስም ብቻ መሆን እንደሌለበት ማስታወስ ያሻል ። ይሁንና የባለቤት ሙያ ጉዳይ በዚህ ብቻ አያልቅም ። ግሥ እላይ እንደ ተጠቀሰው ሁልጊዜ ድርጊትን ብቻ ያመለክታል ለማለት አንችልም ። ለማስረጃ ያህል እንደ ሞተ ፡ ጠፋ ፡ ጠበበ ፡ አጠረ ፡ ወዘተ…የመሳሰሉት ግሦች ሁኔታን እንጂ ድርጊትን እንደማይገልጹ ማስተዋል ያሻል ። ከእንደዚህ ዐይነቶች ግሦች ጋር የሚነገረውም ስም ባለቤት ይባላል ።

ም·5 ቤቱ ሰፋ ።

ም·6 አየለ ጠፋ ።

በተጨማሪም የሚከተለውን ምሳሌ እንመልከት ።

ም·7 ብርጭቆው ተሰበረ ።

ስንል ብርጭቆው የሚለው ከላይ በተጠቀሰው መሠረት ድርጊት ፈጻሚም አስፈጻሚም አይደለም ፤ እንዲያውም የዐረፍተ ነገሩ ፍች እንደሚያመለክተው በብርጭቆው ላይ ድርጊት ተፈጽሟል ። የሆነው ሆኖ በጉልህ የሚታየው የዐረፍተ ነገሩ ባለቤት ብርጭቆው ነው ። ድርጊቱን የፈጸመው ግን አይታወቅም ።

ከዚህም ሌላ ልብ ማድረግ ያለብን ፤ ስም ማለት ከዚህ በፊት እንደ ተለመደው ከበደ ፤ አዲስ አበባ ፤ አዋሽ ፤ በሬ ፤ መሬትና የመሳሰሉት ቃላት ብቻ አለመሆናቸውን ነው ። የሚከተሉትም ከስም ክፍል የሚመደቡ ናቸው ።

1·1·1 ተውላጠ ስም ምሳሌ ፤ እኔ ፤ አንተ ፤ እርሱ ፤ ወዘተ…

ም·8 እኔ ከትምህርት ቤት ተመለስኩ ፤ ወንድሜ ግን ገና መሔዱ ነው ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ እኔ የሚለው ተውላጠ ስም ተመለስኩ ለሚለው ግሥ ባለቤት ነው ። እንዲሁም ወንድሜ የሚለው ስም መሔዱ ነው ለሚለው ግሥ ባለቤት ነው ።

1·1·2 የባለቤት ዝርዝር ፤ ወይንም የባለቤት አጸፋ ፤

ሀ· በማሠሪያ ግሥ ላይ በስተመድረሻ የሚገቡ ኩ ሁ ፤ ክ ህ ፤ ሽ ፤ ኧች ፤ ን ፤ አችሁ ኡ

ም·9 ከዛፉ ላይ ወረድሁ (ኩ)

"ሁ" የሚለው ቅጥያ እኔ በሚለው ተውላጠ

ስም ፈንታ ገብቷል ። እኔ ከዛፉ ላይ ወረድሁ (ኩ) ለማለትም ይቻላል ። ነገር ግን ፡ ቃላት እንደ መደጋገም ስለሚቆጠር ፡ አብዛኛውን ጊዜ የሚመረጠው የላይኛው ዐረፍተ ነገር ነው።

ለ· በቦዝ የሚገቡ ፡ የባለቤት አጸፋዎች ፡ ኤ ፡ ሁ–ሽ ፡ አ ፡ አ ፡–ኧን ፡–አችሁ ፡ ኧው

ምሳሌ 10 እፍርድ ቤት ቀርቤ ነበር ። ቀርቤ በሚለው ውስጥ ኃምሱ ድምፅ እኔ የሚለውን ተውላጠ ስም እንደሚያመለክት ያስተውሏል ።*

ሐ· በዘንድ አንቀጽ ላይ በስተመነሻ የሚገቡ

ም· 11 ተነገ ወዲያ እመጣ ይሆናል ።

ተነገ ወዲያ ትመጣ ይሆናል ተባዕት 2ኛ መደብ

ተነገ ወዲያ ትመጪ* ይሆናል

ተነገ ወዲያ ይመጣ ይሆናል

ተነገ ወዲያ ትመጣ ይሆናል አንስት 3ኛ መደብ

ተነገ ወዲያ እንመጣ ይሆናል

ተነገ ወዲያ ትመጡ* ይሆናል

ተነገ ወዲያ ይመጡ* ይሆናል

እላይ በተጠቀሱት ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ ከግርጌ

---

*በአንደኛ መደብ ነጠላ ቁጥር በሚነገረው ቦዝ አንቀጽ ውስጥ መድረሻው ኃምስ ቀለም ጠብቆ መነበብ ያለበት መሆኑን ማስታወስ ያሻል ።

*ይህ ምልክት ያለባቸው አንቀጾች የሚታወቀው በመነሻም ፡ በመድረሻም ባሉት ባዕድ ቅጥያዎች አማካይነት ነው ።

የተሰመረባቸው ባዕድ ቅጥያዎች የአንቀጹን ባለቤት ያመለክ
ታሉ ።

1·1·3 ጥገኛ ሐረግ

- ጥገኛ ሐረግ የሚባለው ሙሉ ዐረፍተ ነገር ሆኖ ሳለ በማሰሪያ አንቀጹ ላይ ጥገኛ መስተጻምር ስለ ወደቀበት ፡ ዐረፍተ ነገር ለመሆን ያልቻለ በአንድ ስም ሊተካ የሚችል ሐረግ ነው

ም· 12 ከበደ ይመጣል የሚለውን ዐረፍተ ነገር ፡ ወደ ጥገኛ ሐረግ ብንለውጠው ከበደ እንደሚመጣ ወይንም የከበደ መምጣት ሊሆን ይችላል ።

ከበደ እንደሚመጣ የሚለውን የዐረፍተ ነገር ባለቤት ብናደርገው ፡

ም· 13 ከበደ እንደሚመጣ ታውቋል ።

የሚል ዐይነት የተሟላ ዐረፍተ ነገር መሥራት ይቻላል ። "ታውቋል" የሚለውን ማሰሪያ አንቀጹን ባንለውጥ ፡

ከበደ እንደሚመጣ በማለት ፈንታ ፡

ም· 14 ሥራው ታውቋል ማለት እንችላለን ። እዚህ ላይ ከበደ እንደሚመጣ የሚለው ጥገኛ ሐረግና ሥራው የሚለው ስም ተመጣጣኝ መሆናቸው ነው ።

እንዲሁም

ም· 15 የከበደ መምጣት አስገረመኝ ብንል ፡

የከበደ መምጣት የሚለው ሐረግ እንደ ባለቤት ማገልገሉን ያስተውሏል ። በሚከተሉት ምሳሌዎች ውስጥ ከየግርጌያቸው የተሠመረባቸው ጥገኛ ሐረጎች ባለቤት መሆናቸውን አስተውል ።

–ም. 16 መጽሐፉን ደኅና አድርጎ ያነበበ ይሸለማል ።

–ም. 17 መምህሩ ወደፊት እንደሚያስተምሩ ተገለጸ ።

ም. 18 የሠራ ያገኛል ፤ ያልሠራ ይቸገራል ።

1·1·4 አርእስት (ንኡስ አንቀጽ)

እርእስት የምንለው በሌሎች የሰዋስው መጻሕፍት የግሥ ሥር ፡ መሠረት ነው እየተባለ የተገለጸውን ቃል ሲሆን ፤ እኛ ግን ከግሥ የሚገኝ ስም ብለን የምንጠራው በስተመን ሻው "መ" የተባለ ባዕድ ቅጥያ ያለውን ቃል ነው ።

አጅ ፡

መሔድ ፡ መሮጥ ፡ ማልቀስ ፡ ማዘን ወዘተ...

የዚህ ዐይነቱ ቃል ባለቤት ሲሆን እንደሚከተለው ይሆናል ።

ም.19 መሔዱ ይወራል ።

አርእስት ከስም ጋር ሲነገር አርእስታዊ ሐረግ ይሆናል ።

አጅ የከበደ መሔድ ፡ የዋናው ሹም መምጣት ፡ የምርታችን ማደግ ወዘተ...

1.1.5 ቅጽላዊ ጥገኛ ሐረግ

- ግሡ ከማሰሪያነት የታገደ ዐረፍተ ነገር እንደ አንድ ቅጽል ሆኖ ስምን ሊገልጽ ይችላል ። እንዲያ ያለውን ሐረግ አንዳንድ የሰዋስው አዘጋጆች ቅጽላዊ ጥገኛ ሐረግ ይሉታል ።

ም.20 ባለፈው ወር ከዘመቻ የተመለሰው ወታደር ተሸለመ ።

እንግዲህ በዚህ ምሳሌ ውስጥ ከግርጌው የተሠመረበት ሐረግ ቅጽላዊ ጥገኛ ሐረግ መሆኑን አስተውል ።

ማጠቃለያ፡ ከዚህ በላይ እንዳየነው በዐረፍተ ነገር ውስጥ ባለቤት ሊሆን የሚችለው እንደ ከበደ ፡ ፈረስ፡ ዛፍ ፡ ቤት ፡ አዋሽ ፡ ወዘተ… የመሰለው ነጠላ ስም ብቻ ሳይሆን እንደነዚህ ያሉትን ስሞች ሊተካ የሚችል ሁሉ ነው ።

አጅ ፡ ተውላጠ ስም ፡ ግሣዊ አጸፋ ፡ አርስታዊ ሐረግ ቅጽላዊ ጥገኛ ሐረግ ወዘተ…

## አንደኛ መልመጃ

በሚከተሉት በያንዳንዱ ዐረፍተ ነገር ወይንም ሐረግ ውስጥ ባለቤቱ የትኛው እንደሆነ አሳይ ።

1. ከቤታችን ግርጌ ትልቅ ወርካ ዛፍ አለ ።
2. የምትፈልጉትን ሁሉ ሳትወስዱ ቀራችሁ ።
3. እኔና ወንድሜ በዘበኝነት እናገለግላለን ።
4. አፍ እንዳመጣ መቀባጠር ደንቆሮ ያሰኛል ።
5. አቶ ከበደ ሲለፋበት የነበረው ሁሉ መና ሆኖ ቀረ ።
6. ወንድማችን እንደ ተፈለገ ዐወቀ ።
7. ስለ ወንድሙ መምጣት ነግሮት ነበር ።
8. የልጅ ልጄ መሬቱን ለማልማት ብዙ ከደከመ በኋላ ።
9. ዛፍ በመጥረቢያ መቁረጥ ትችላለህ ።
10. ራስን ደኅና አድርጐ ማወቅ ብልህ ያሰኛል ።

### 1.2 ቀጥተኛ ተሳቢ

#### 1.2.1 ባረፍተ ነገር ውስጥ የቀጥተኛ ተሳቢ ቦታ

-ቀጥተኛ ተሳቢ የምንለው በግሥ የተጠቀሰው ድርጊት የሚፈጸምበትን ስም ወይንም ሐረግ ነው ።

አብዛኛውን ጊዜ ቀጥተኛ ተሳቢ የሚገኘው ከባለቤቱ ቀጥሎ ነው ። (ማለት ባለቤቱ ቀድሞ ቀጥተኛ ተሳቢው ይከተለዋል ።)

ምሳሌ ፡

ም.21 አህያ ሣር ይበላል ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ "ሣር" ቀጥተኛ ተሳቢ ነው ፡ የሚገባውም የዐረፍተ ነገሩ ባለቤት ከሆነው "አህያ" ከሚለው ቃል ቀጥሎ ነው ።

ነገር ግን

ም.22 ሣር አህያ ይበላል

ብንል በሸዋስው ሥርዓት "አህያ" ቀጥተኛ ተሳቢ መሆኑ ነው ። ይህንንም በፍች በኩል ያየነው እንደሆነ ከትክክለኛ አስተሳሰብ ጋር የማይጣጣም ሆኖ እናገኘዋለን ። ሌላ ምሳሌ እንመልከት ።

ም.23 ንብ አበባ ይቀስማል ።

ማለት ስንችል

ም.24 አበባ ንብ ይቀስማል

ብንል እላይ እንደ ተጠቀሰው የማያስኬድ ሆኖ እናገኘዋለን ። ስለዚህ እንዲህ ባሉት ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ ቀጥተኛው ተሳቢ ባለቤቱን ተከትሎ መምጣት አለ

በት ማለት ነው ።

ይሁንና ቀጥተኛ ተሳቢው ከባለቤት ቀድሞ ቢገኝም የሚያስኬድበት ጊዜ አለ።

ም.25 ከበደ በቀለን መታው ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ቀጥተኛ ተሳቢው በቀለ መሆኑ ጉልህ ነው ።የገባውም ባለቤቱን ተከትሎ ነው ። ነገር ግን ባለቤቱን ቀድሞ ሊገባም ይችላል ።

ም.26 በቀለን ከበደ መታው ።

አህያ ሣር ይበላል በሚለውና ከበደ በቀለን መታው በሚለው መካከል ያለው ልዩነት ምንድነው ብለን ራሳችንን ብንጠይቅ ፣ መልሱ በላይኛው ዐረፍተ ነገር ቀጥተኛ ተሳቢው (ሣር) ያልተወሰነ (ዕውቅ ያልሆነ) ሲሆን ፣ የኋለኛው ቀጥተኛ ተሳቢ ግን (በቀለ) የተወሰነ (ዕውቅ) ነው የሚል ይሆናል ።

ስለዚህ ቀጥተኛ ተሳቢው ዕውቅ ባልሆነ ጊዜ ውሎው ከባለቤቱ ቀጥሎ ነው ። ዕውቅ ሲሆን ግን ባለቤቱን ሊቀድምም ሊከተልም ይችላል ። በተጨማሪም የተወሰነው ቀጥተኛ ተሳቢ በስተመድረሻው "ን" እንደሚያሻው ማስተዋል ይገባል ።

ማስታወሻ

ከፍ ብለን ቀጥተኛ ተሳቢ ድርጊት የሚፈጸምበት ስም ወይንም ሐረግ እንደሆነ ተናግረን ነበር ። በሰጠናቸውም ምሳሌዎች ውስጥ ማር ፣ አበባ ፣ በቀለ ፣ በተባሉት ስሞች ላይ ድርጊቱ ተፈጽሞባቸዋል ። ይሁን እንጂ ፣ ይህ ሰዋስዋዊ ዐዋጅ ሁልጊዜ የጸና አይሆንም ።

ለ.ም:

ሀ. አየለ እንግሊዝኛ ተማረ

ለ. ደመቀ አባቱን መሰለ

ሐ. ልጁ ወንድሙን ይወዳል።

መ. አስተማሪያችን ደራሲውን አደነቀ ።

በግርጌያቸው የተሰመረባቸው ስሞች ቀጥተኛ ተሳቢዎች ይሁኑ እንጂ ድርጊቱ ተፈጸመባቸው ለማለት ያዳግታል።

## 1.2.2 በቀጥተኛ ተሳቢ ላይ "ን" የማያስፈልግበትና የሚያስፈልግበት ጊዜ

ሀ. የማያስፈልግበት ጊዜ

ቀጥተኛ ተሳቢው ዕውቅ ወይንም የተወሰነ ካልሆነ በስተቀር በስተመድረሻው ላይ የቀጥተኛ ተሳቢ ምልክት "ን" አስፈላጊ አይሆንም ።

ምሳሌ ፡

ም.27 ልጁ ጫማ አድርጓል ።

ም.28 ፈረሱ ጥሬ ይወዳል ።

ም.29 አበጀ መሮጥ ይፈልጋል ።

ም.30 ቤት መሥራት ይወዳል ።

እላይ በተመለከትናቸው ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ ያሉት ቀጥተኛ ተሳቢዎች ጫማ ፡ ጥሬ ፡ መሮጥና ቤት መሥራት የተወሰኑ ወይንም የታወቁ የሚያደርጓቸው ምልክቶች ስለሌሏቸው "ን" አላስፈለጋቸውም ።

አንዳንድ የሰዋስው አዘጋጆች[1] "ን" በማንኛውም ቀጥተኛ ተሳቢ መድረሻ ላይ እንደሚያስፈልግ ይናገራሉ ።

በዚህም ሁኔታ እላይ የተጠቀሱት ዐረፍተ ነገሮች እንደሚከተለው መሆናቸው ነው ።

ም. 31 ልጁ ጫማን አድርጓል ።

ም.32 ፈረሱ ጥሬን ይወዳል ።

ም.33 አበጀ መሮጥን ይፈልጋል ።

ም.34 ቤት መሥራትን ይወዳል ።

ነገር ግን አፍ መፍቻ ቋንቋቸው አማርኛ የሆኑ ሰዎች በዚህ መንገድ ሲናገሩ አንሰማም ። ስለዚህ "ን" ን በማንኛውም ቀጥተኛ ተሳቢ ላይ አስገባ የሚል ዐዋጅ ለአማርኛ ቋንቋ አይስማማውም ማለት ነው ።

እዚህ ላይ ማስተዋል ያለብን የሰዋስው መጽሐፍ

---

1 ለምሳሌ መርስዔሐዘን ወልደ ቂርቆስ የማርኛ ሰዋሰው ፡ ገጽ 37 39 ፡ 1948 ተክለማርያም ፋንታዬ ጥንተ ጥበብ ዘሥን ጽሑፍ

አዘጋጅ የቋንቋው ባለቤቶች የሚናገሩትን መሠረት አድርጎ ሕግ ማውጣት እንደሚገባው እንጂ ፡ እሱ የፈጠረው ሕግ የቋንቋውን መሠረታዊ ሥርዓት ሊለ ውጥ እንደማይችል ነው ። የቋንቋውም መሠረታዊ ሥር ዓት የቋንቋው ተናጋሪዎች የሚከተሉት የተለመደ ያነጋገር ስልት መሆኑ አይጠረጠርም ።

ለ. የሚያስፈልግበት ጊዜ

ቀጥተኛ ተሳቢ "ን" የሚያስፈልገው ዕውቅ ሲሆን ወይንም የተወሰነ አመልካች ሲኖርበት ነው ። ዕውቅ የሚሆነውስ እንዴት ነው?

1ኛ የተጸውኦ ስም ሲሆን

ምሳሌ ፡ አበበ ፡ ከበደ ፡ አዲስ አበባ ፡ ተከዜ ወዘተ... እንደነዚህ ያሉት ስሞች ቀጥተኛ ተሳቢ በሚሆኑበት ጊዜ በመድረሻቸው "ን" የግድ ያስፈልጋቸዋል።

ም.35 አበበ ከበደን አየ ።

ም.36 አዲስ አበባን የማይወድ የለም ።

ም.37 ከወንዞቹ ሁሉ ተከዜን አላውቅም ።

እላይ በተሰጡት ምሳሌዎች ውስጥ የገባው የቀጥተኛ ተሳቢ ምልክት "ን" ቢቀር ኖሮ ፡ ንግግሩ የተዛባ ሊሆን እንደሚችል ማስተዋል አያዳግትም ። ይኸውም ፡

ም.38 አበበ ከበደ አየ

ም.39 አዲስ አበባ የማይወድ የለም ።

ም.40 ከወንዞች ሁሉ ተከዜ አላውቅም እንደ ማለት ነው ።

2ኛ መስተኣምር ሲኖረው

**መስተአምር** የሚባለው ከስም በስተመድረሻ እየገባ ያ ስም ከዚህ በፊት የታወቀ ወይንም የተለየ መሆኑን የሚያመለክት ባዕድ ቅጥያ ነው ። ባማርኛ የመስተአምርነት ሞያ ያላቸው ባዕድ ቅጥያዎች የሚከተሉት ናቸው።

| ተባዕት | እንስት |
|---|---|
| ኡ/ው/* | ዋ |
| | ኢቱ ዩቱ ፡ ኢቷ/ ዩቷ |
| ዩው | ዩዋ |

ምሳሌ ፡

ም.41 አበበ አጐቱን አነጋገራቸው ።

ም.42 ዘበኛውን ዛሬ አላየሁትም ።

ም.42 አባትየውን አከብራቸዋለሁ ።

ም.43 በጓን (በግዋን) አረዳት ።

ም.44 ፍየሊቱን እዛፉጋ አሰራት ።

ም.45 እኅትዩዋን አውቃታለሁ ።

እላይ በተጠቀሱት ምሳሌዎች ውስጥ የሚገኘው "ን" ቢገደፍ ኖሮ ዐረፍተ ነገሮቹ የተሣቡ እንደሚሆኑ አስተውል ።

ም.46 ሰዎቹ ምሳ አብላቸው አይባልም።

3ኛ/ የተወሰነ አመልካች ፡ መስተአምር ወይንም አመልካች ተውላጠ ስም ቀጥተኛ ተሳቢ ሲሆን

| ተባዕት | እንስት | የብዙ ቁጥር |
|---|---|---|
| ይህ | ይህች(ይች) | እነዚህ |

*ኡ ከናባቢ በኋላ ሲመጣ "ው" ይሆናል ፡ ምሳሌ በቅሎኡ በቅሎው "ኢቱ" ከናባቢ በኋላ ሲመጣ "ዩቱ" ይሆናል ፡ ምሳሌ በቅሎ በቅሎኢቱ በቅሎዩቱ

ያ ያች እነዚያ
ይኸኛው ይችኛዋ እነዚኸኞቹ ፡ እነኝህ
ያኛው ያችኛዋ እነዚያኞቹ ፡ እነኛ

ም.47 ይህን እርሳስ ውሰድና ያን ስጠን ።
ም.48 ይህችን /ይችን/ ሴት እርዳልኝ ።
ም.49 እነዚያን ሰዎች አስጠራልኝ ።
ም.50 ያነጋገርኩት ያኛውን እንጂ ይኸኛውን አይደ
ለም ።
ም.51 እነኛን አስተማሪዎች ልጋብዛቸው እፈልጋለሁ ።

እነሆ ከነዚህ ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ ከቀጥተኛ ተሳ
ቢው ላይ "ን" ቢነሣ ዐረፍተ ነገሮቹ የተዛቡ ይሆናሉ ።
ም.52 "ይህ እርሳስ ውሰድና ያ ስጠኝ" አይባልም ።
ማስታወሻ፣ በተወሰነ አመልካች መስተአምር የሚገ
ለጽ ቀጥተኛ ተሳቢ ዐጸፋ መስተአምር ያለው እንደሆነ
"ን" በሁለቱም ላይ ይገባል ።
ም.53 ይህን ልጅህን ቅጣ ።
ም.54 ነገር ግን
ም.55 ይህን ልጅህ ቅጣ
ይህ ልጅህን ቅጣ አይባልም
4ኛ/ አገናዛቢ አጸፋ ያለው ስም ቀጥተኛ ተሳቢ ሲሆን
አገናዛቢ ዐጸፋ የምንለው ከስም በስተመድረሻ
እየገባ ባለገንዘብነትን የሚያመለክተውን ባዕድ ቅጥያ
ነው ። አገናዛቢ ዐጸፋዎች የሚባሉት የሚከተሉት
ናቸው ።

| ነጠላ | ብዙ |
|---|---|
| — ኤ (ዬ)* | — አችን |
| — ህ /ክ/ | |
| ሽ | — አችሁ |
| — ኡ /ው/* | — አቸው |
| — ዋ | |

ም.56 ወይፈኔን ለሠላሳ ብር ሸጥኩት

ም.57 ቤትህን አሳየኝ ።

ም.58 አገራችሁን ውደዱ ።

ም.59 ልብስሽን እጠቢ ።

ም.60 ገንዘባቸውን ይቆጥባሉ ።

5ኛ/ ዘርፍ ያለው ስም ቀጥተኛ ተሳቢ ሲሆን

- ዘርፍ የሚባለው በስተመነሻው "የ" የወደቀበት ሌላውን ስም ለመግለጽ በቅጽልነት ሞያ የሚያገለግል ስም ነው።

ም.61 የከበደን ፈረስ ጋለብኩት ።

ም.62 የስተማሪውን ልጅ አጫውታለሁ ።

ማስታወሻ ፡ አንዳንድ ያፍ መፍቻ ቋንቋቸው አማርኛ ያልሆነ ተማሪዎች "ን"ን ከዘርፉ ባለቤት በስተመድረሻ የሚያገቡበት ጊዜ አለ ።

ም.63 የከበደ ፈረስን ጋለብኩት

እንደዚህ ያለው አነጋገር በአማርኛ ስሕተት ነው ።

---

* ከአናባቢ በኋላ "ኤ" ወደ "ዬ" ይለወጣል ፡ እንዲሁም "ኡ" ወደ "ው" ይለወጣል ። ምሳሌ ፡ በሬኤ በሬዬ ፡ ዶሮኡ ዶሮው

ዐዋጅ ፡ መስተአምር ያለበት ቅጽላዊ ጥገኛ ሐረግ በተሳቢነት ሲገባ ወይንም የተሳቢ ገላጭ ሲሆን ፡ በስተመድረሻው "ን" ያስፈልገዋል ።

ም.64 የተሰበረውን ብርጭቆ አውጥተህ ጣል ።

6ኛ ምድብ ተውላጠ ስም

እኔ ፡ አንተ ፡ አንቺ ፡ እርሱ ፡ እርሷ ፡ ወዘተ...

ም.65 አስተማሪያችን እሱን ይወደዋል እኔን ግን የሚጠላኝ ይመስለኛል ።

ም.66 እናንተን ስላላገኘሁ ፡ ለወንድማችሁ ነግሬ ሔድኩኝ ።

ም.67 እኅትሽ እስብሰባው ላይ ነበረች ፡ አንቺን ግን አላየሁሽም ።

ማስታወሻ ፡ የ"ን" አገልግሎት ቀጥተኛ ተሳቢን ማመልከት ብቻ አለመሆኑን ማስተዋል ያሻል ።

ም.68 ብቻውን ነው ።

ም.69 ሜዳ ሜዳውን ሔደ ።

ም.70 ቁልቁለቱን ወረደ ወዘተ...

በነዚህ ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ "ን" አገልግሎቱ እንደ መስተዋድድ እንጂ ፡ እንደ ቀጥተኛ ተሳቢ አመልካች አይደለም የተባለበት እነዚህን ዐረፍተ ነገሮች ሐሳባቸውን ሳንለውጥ በሚከተለው ሁናቴ መስተዋድድ በማስገባት ልንናገራቸው ስለምንችል ነው ።

ም.71 ለብቻው ነው

ም.72 በሜዳ በሜዳው ሔደ

ም.73 በቋልቋለቱ ወረደ.

በነዚህ ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ በግርጌያቸው የተሠመረ ባቸው መስተዋድዶች ናቸው ።

ሁለተኛ መልመጃ

በሚከተሉት ዐረፍተ ነገሮች ውስጥ "ን" በማያስፈል ግበት ቦታ ገብቶ በሚያስፈልግበት ቦታ ደግሞ ተገድፏል ። እያስተካከልክ ጻፍ ።

1. መኪናን የሚነዳ ሰው እነሆ አሁን መጣ ።
2. የከበደ መጽሐፉን ሳነብ ነበር ።
3. አሻግሬ ይህ ዐመሉን እንደማልወድ እያወቀ አልተው አለኝ ።
4. በፔርክልስ ዘመነ መንግሥት በአቴና የነበሩ ሥዕል ሠዓሊዎችና ሐውልት የሚቀርፁ አርቲስ ቶች ሲሠሩዋቸው የነበሩት ሥራዎች በታሪክ ስንመለከት ፣ ግሪክ በሥነ ጥበብ ከመጨረሻው ከፍተኛ ደረጃ ደርሳ እናገኛታለን ።
5. ሐኪም የታመሙትን ቢያክም ፣ የተራቡት አያበላ ቸውም ።
6. እኔ በበኩሌ የኢትዮጵያ ታሪክ ሳነብ ፣ ያፄ ምኒልክ ሥራ ሳላደንቅ አላልፍም ።
7. ጓደኛዬ በየመንገዱ አጠገብ የሚገኙት የተራራዎ ችና የወንዞች ስም ይነግረኝ ነበር ።
8. በሌላ አገር የታወቀው መሻሻልና ሥልጣኔ በመቅ ሰም ለአገር ለሚጠቅመውን ለመሥራት አዳጋች አይሆንም ።

9. በእጅ የሚሠሩትን ነገሮች በመኪና በመሥራት ቸው ብዙ ዓመታት የሚወስደውን በአጭር ጊዜ ውስጥ ይከናወናል ።
10. ትክክለኛውን የሰውዬው ታሪክ አልተገለጸም ።
11. ንግግሯ ሳትጨርስ "እናቴ ይልቅ የሚያስፈልገኝ ነገር ብታዘጋጅልኝ ይሻላል" አላት ።
12. እኛም የእርሱን ደግነት ትዝ እያለን ለራሳችንና ለአገራችን ጠቃሚ የሆኑ ነገሮችን ለመሥራት ችለናል ።
13. ይህንን ንግግራቸው በትእምርተ ጥቅስ ውስጥ መግባት ነበረበት ።
14. ማንም ሰው ይህን ጽሑፋቸው ሲያነብ እጦርነቱ ቦታ ቆሞ የሚመለከት ይመስለዋል ።
15. ሁሉም ነገር ራሴ ለመምረጥ እፈልግ ጀመር ።

## 1.3. የመስተዋድድ ተገኝር

እስካሁን የተነጋገርንባቸው የስም ሞያዎች ባለቤትና ቀጥተኛ ተሳቢ ናቸው ። ቀጥለን ደግሞ ፡ ስለ ሦስተኛው ዐይነት የስም ሞያ ስለ መስተዋድድ ተገኝር እንነጋገር ።

የመስተዋድድ ተገኝር ማለት መስተዋድድ የወደቀበት ስም ማለት ነው ። ለባለቤትና ለቀጥተኛ ተሳቢ እንደ ተነገረው ሁሉ መስተዋድድ የሚገባው በስም ላይ ብቻ ሳይሆን እንደ አርእስት ፡ እንደ ተውላጠ ስም ፡ እንደ አርእስታዊ ንኡስ ሐረግ ወዘተ ... በመሳሰሉትም ላይ ነው ።

እጅ ፡ በስም ላይ ሲወድቅ ፡ በመጥረቢያ ፡ በብዕር ፡

ለበቀለ ፡ እንደ አጥናፉ ከአዲስ አበባ ወዘተ …

በአርእስት ላይ ሲወድቅ ፡ እንደ መጻፍ ፡ እንደ ማንበብ ፡ ለመሔድ ፡ ለመሮጥ ወዘተ…

በተውላጠ ስም ላይ ሲወድቅ ፡ በኔ ፡ በሱ ፡ እንዳንተ ፡ ከኛ ፡ ወዘተ … ተማሮችም ሆኑ አንዳንድ የማይጠነቀቁ ደራሲያን መስተዋድዱን በመግደፍ የመስተዋድድ ተገዥ ሊሆን የሚገባውን ስም ወይንም ሐረግ እንደ ባለቤት በማስመሰል ስሚን ወይንም አንባቢን ያደናግራሉ ።

ለምሳሌ ፡ “አለባበሱና ሁኔታው ሁሉ የጨዋ ልጅ ይመስላል”

በዚህ ዐረፍተ ነገር “የጨዋ ልጅ ይመስላል” የተባለው ማነው? ወይንም ምንድን ነው? ብለን ብንጠይቅ ፡ የምናገኘው መልስ ምናልባት አለባበሱና ሁኔታውን እንደሆን ነው እንጂ ሌላ መልስ ከዐረፍተ ነገሩ ውስጥ አናገኝም ። መልሱም ይህ ነው እንዳንል ትርጉሙ አይሰደንም ። የሆነው ሆኖ ፡ በተጠቀሰው ዐረፍተ ነገር ሰውዬው ለማለት የፈለገው የሚከተለውን ነው ።

“ባለባበሱና በሁኔታው ሁሉ የጨዋ ልጅ ይመስላል”

እዚህ ላይ ምንም እንኳ ባለቤቱ ማን እንደሆነ ግልጽ ባይሆንም ፡ ከዚህ በፊት የተጠቀሰ አንድ ሰው መሆኑን ለመገመት አያዳግተንም ። ያም ሆነ ይህ ፡ “አለባበሱና ሁናቴው ሁሉ” የሚለው ሐረግ ፡ መስተ

ዋድድ ካልወደቀበት በስተቀር ምንም አገልግሎት የሌለው መሆኑ ግልጽ ነው ። በዚህ ዐይነት ብዙ ተማሪዎች መስተዋድድ በመግደፍ "አየለ ቤት ነው" "ልጇ ዛፉ ጋ ነው ፡ ቤት እሔዳለሁ" እያሉ ይጽፋሉ ። ሌላው ዐይነት ስሕተት ደግሞ ፡ የክሩ መተርጐሚያ ተብሎ የተሠየመውን "በ"ን ሳያስፈልግ ማስገባት ነው ።

ም.74 በአንድ ቢላዋ ዳቦውን ቆረጠበት ።

እንደዚህ ያለውን ዐረፍተ ነገር የሚሠራ ሰው ያልተገነዘበው ነገር ያለ/ይመስላል ። ይኸውም "በአ ንድ ቢላዋ ዳቦውን ቆረጠበት" ሲል ፡ ቢላዋው አንድ ያልተፈለገ ሥራ እንደ ተፈጸመበት አድርጎ ማቅረቡ ነው ። ለምሳሌ ፡ "በከበደ ቀለደበት" እንደ ማለት ያህል ነው ። እነሆ የመጀመሪያውን ዐረፍተ ነገር በዚህ መንገድ የተመለከትነው እንደሆን ፡ ከበደ መቀለጃ እንደሆነ ሁሉ በቢላዋው ላይ ተመሳሳይ የማይፈለግ ድርጊት እንደ ተፈጸመበት ያህል መቆጠሩ ነው ። ነገር ግን ዐረፍተ ነገሩን የሠራው ሰው እንዲህ ያለ ሐሳብ በአዕምሮው ያለ አይመስልም ። እንዲያ ለማለት ከፈለገም ፡

ም.75 በቢላዋው ዳቦውን ቆረጠበት ማለት ይኖርበት ነበር ።

ነገር ግን ፡ ሊገለጽ የተፈለገው ሐሳብ አንድ ሰው በአንድ ዕውቅ ባልሆነ ቢላዋ ዳቦ መቁረጡን ከሆነ ፡ ዐረፍተ ነገሩ እንደሚከተለው ሆኖ መስተካከል አለ በት።

ም.76 በአንድ ቢላዋ ዳቦውን ቆረጠ

አንዳንድ ተማሪዎች ፡

ም. 77 ለብርሃኑ የተባለ ልጅ መጽሐፉን ሰጠሁት ።

የሚል ዐይነት ዐረፍተ ነገር ሲጽፉና ሲናገሩ ይገኛሉ ። እዚህ ላይ ያልተገነዘቡት የመስተዋድድ ተገኝ ገላጭ ቢኖረው ፡ በተለይም ገላጩ ግልጸ "የ" ሲሆን ፡ መስተዋድዱ የት ላይ ሊገባ እንደሚገባው ነው ።

ግልጸ "የ" ም የምንለው "የጠቆረ" ፡ "የጠነከረ" የሚለውን ዐይነት ሐረግ ነው ። እንዲህ ያለ ገላጭ ያለው የመስተዋድድ ተገኝ ሲያጋጥም መስተዋድዱ የሚገባው ከግልጸ "የ" ው በፊት መሆን አለበት ፡ እንዲህም ሲሆን "የ" ውስጠ ታዋቂ ሆኖ ይገደፋል ።

አ፦ ፡ የመጣ ሰው ፡ የደከመ ሰው ፡ በሚል ዐይነት ሐረግ ላይ መስተዋድድ ሲጨመርበት ፡ ለመጣ ሰው እንደ ደከመ ሰው ይሆናል ። ይህም ሲሆን "የ" መቅረቱን ማስተዋል ያሻል ። ማለት ለየመጣ ሰው እንደ የደከመ ሰው አንልም ማለት ነው ።

ነገር ግን ፡ ከፍ ብሎ በተጠቀሰው የዐረፍተ ነገር ዐይነት ውስጥ በገላጩና በተገላጩ ቃል መካከል የቦታ መለዋወጥ ስላለ ፡ ሁናቴው ትንሽ ለየት ያለ ይመስላል ።

አ፦ ፡ ከበደ የተባለ ልጅ

ጐንደር የተባለ ከተማ

ወዳጄ የሆነ ሰው ስንል ግልጸ "የ" የሆነው ገላጭ የገባው ከተገላጩ በኋላ ነው ። ስለዚህ መስተዋድዱም ከርሱ ማለት ከገላጩ በፊት ይገባል ማለት ነው ።

በአጠቃላይ አነጋገር መስተዋድድ የሚገባው ሁልጊ

ዜም ከገላጩ በፊት ነው ። ግልጸ "የ" ም ያለበት ገላጭ ሲያጋጥም መስተዋድዱ የሚወድቀው በግልጸ "የ" ው ላይ ነው ። ይህም ሲሆን "የ" ተገድፎ ይቀራል ወይንም መስተዋድዱ በርሱ ቦታ ይተካል ።

ም. 78 ብርሃኑ ለተባለ ልጅ እንላለን እንጂ ፡ ለብርሃኑ የተባለ ልጅ አንልም ። ባጭሩ ግልጸ "የ" የትም ቦታ ቢገባ መስተዋድድ እንዲጨመርበት ካስፈለገ የሚገባው በ "የ" ቦታ ነው ።

እንደገና ሌሎች ምሳሌዎች እናምጣ ።

ም. 79 ለመጽሐፍ ፍለጋ የመጣ ተማሪ በማለት ፈንታ ፡ መጽሐፍ ፍለጋ ለመጣ ተማሪ እንላለን ።

ም. 80 ወደ ጐንደር ተብሎ የተሠየመ ከተማ የሚለውን ጐንደር ተብሎ ወደ ተሠየመ ከተማ ማለት አለብን ።

ማስታወሻ ፡

ስለ መስተዋድድ ተገኘ እስካሁን የተነገረው ይበቃል። በድጋሚ ለማስታወስ ያህል ፡

1. መስተዋድድ ሳይፈለግ እንዳይገባ መቆጣጠር
2. በሚያስፈልገበት ጊዜ ደግሞ ተገድፎ እንዳይቀር መጠንቀቅ
3. መስተዋድድ ሲያስፈልግ ያለቦታው እንዳይገባ መጠንቀቅ ያሻል ።

## 1.4 ተጣማሪ

ተጣማሪ የሚባለው ባለቤቱን ፡ ቀጥተኛ ተሳቢውን ወይንም የመስተዋድዱን ተገኘ ለማብራራያ ያህል የሚጨመር ስም ወይንም ሐረግ ነው ።

ም. 81 ከበደ ፡ [illegible]

ትምህርት ፡ እንግሊዝ ፡ን በይበልጥ ያጠናል ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ወ ስጥ ያሉት ተጣማሪዎች ሁለት ናቸው ። እነሱም

1ኛ/ ለባለቤቱ ለከበደ ተጣማሪ የሆነው <u>የማሚቱ ልጅ</u> የሚለው ሐረግና

2ኛ/ የሚወደውን ትምህርት ለሚለው ቀጥተኛ ተሳቢ ተጣማሪ የሆነው <u>እንግሊዝኛ</u> የሚለው ስም ናቸው ።

እዚህ ላይ ማስተዋል ያለብን ተጣማሪ የተባለው ትርፍ ነገር መሆኑንና ባይኖርም ዐረፍተ ነገሩ በሰዋስው ረገድ የተሟላ መሆኑን ነው ።

<u>ለምሳሌ ፡</u> ከላይ በተጠቀሰው ዐረፍተ ነገር ውስጥ ተጣማሪዎ ቹን ብናነሣ ዐረፍተ ነገሩ ፡

ም. 82 ከበደ የሚወደውን ትምህርት በይበልጥ ያጠናል

የሚል ይሆናል ። ስለዚህ የተጣማሪዎቹ አገልግሎት ባለቤቱ ንና ቀጥተኛ ተሳቢውን ለይቶና ወስኖ ማመልከት ነው ።

<u>ለምሳሌ</u> ፡ ከበደ ሲል የትኛው ከበደ የሚል ጥያቄ እንዳይነሣ በተለይም ብዙ ከበደዎች ያሉ እንደሆን ፡

"የማሚቱ ልጅ" የሚለው ጥያቄውን ይመልሳል ። እንዲሁም የሚወደውን ትምህርት ቢባል ፡ የትኛውን ትምህ ርት የሚል ጥያቄ ሊነሣ ስለሚችል "እንግሊዝኛ" የሚለው ተጣማሪ ይህን ጥያቄ ይመልሳል ማለት ነው ።

አንዳንድ ተማሪዎች ለተወሰነ ቀጥተኛ ተሳቢና ለመስ ተዋድድ ተገኘr የሚገባቸውን "ን" ወይንም መስተዋድዶ ቹን በመግደፍ የሚከተሉትን ዐይነት ዐረፍተ ነገሮች ይጽ

ፉሉ ።

ም. 83 ከበደ የማሚቴ ልጅ በጣም የሚወደውን ትምህርት

እንግሊዝኛ በደብልዋ ያጠናል ።

ም. 84 መምህሩ ለከበደ ጉበዝ ተማሪ ሽልማት ሰጥቷል ።

እዚህ ላይ ልናስታውሰው የምንፈልገው በቀጥተኛ ተሳቢ ላይ የሚወድቀው ፡ የቀጥተኛ ተሳቢ ምልክት "ን" በተጣማሪውም ላይ መግባት ያለበት መሆኑንና እንዲሁም የመስተዋድዱ ተገኘ ተጣማሪ ካለው በተጣማሪውም ላይ መስተዋድድ የሚያስፈልግ መሆኑን ነው ።

ም. 85 ለከበደ ለጉበዙ ተማሪ እንጂ

ለከበደ ጉበዙ ተማሪ አይባልም ።

ወይንም

ም. 86 በጣም የሚወደውን ትምህርት እንግሊዝኛን ያጠናል

እንጂ ፡

በጣም የሚወደውን ትምህርት እንግሊዝኛ ያጠናል

አይባልም ።

እንዲሁም

ም. 87 ለአባቴ ለአቶ ከበደ መንገሻ እንጂ

ለአባቴ አቶ ከበደ መንገሻ አይባልም ።

1.5 መሙያ

የዐረፍተ ነገሩ ማሰሪያ አንቀጽ የመሆን ግሥ ሲሆን ፡ ከግሡ በፊት የሚገባው ስም ፡ ቅጽል አለዚያም ስምን ሊተካ የሚችል ቃል ወይንም ስማዊ ሐረግ መሙያ ይባላል ።

ም. 88 አየለ አስተማሪ ነው ።

ም. 89 ቤቱ በጣም ትልቅ ነው እንደ ማለት ነው ። በነዚህ ምሳሌዎች ውስጥ "አስተማሪ" የሚለው ስምና "በጣም

ትልቅ” የሚለው ሐረግ መሙያዎች መሆናቸው ነው ።

እዚህ ላይ መሙያ የተባለውን የስም ሞያ የጠቀስነው ከስም ሞያዎች አንዱ ክፍል ስለሆነ ፡ ለማስታወስ ያህል እንጂ ስዋስዋዊ ስሕተት ያደርግበታል ለማለት አይደለም ።

ማጠቃለያ ፡ እስካሁን ስለ ልዩ ልዩ የስም ሙያዎች ተነጋግረናል ። በተነጋገርነው መሠረት የሚከተለውን ያንድ ተማሪ ዐረፍተ ነገር እንመርምር ።

ም· 90 በከተማው ውስጥ የምንኖር ሰዎች በመርዝ ጢስ ታፍነን የተጣራ አየር ባለማግኘት ሰውነታችን በሽተኛ በመሆኑ በየስፍራው ሆስፒታሎችን እንዲቋቋም አድርጓል ።

የዚህ ዐረፍተ ነገር ጉድለት ምንድነው? ጐልቶ የሚታየው ጉድለት “ሆስፒታሎችን እንዲቋቋም አድርጓል” ለሚለው ሐረግ ባለቤቱ የቱ እንደሆነ አለመታወቁ ነው ። በሌላ አነጋገር ባለቤት የጐደለው ዐረፍተ ነገር ብለን ልንጠራው እንችላለን ። ምናልባት ደራሲው በሐሳቡ በዐረፍተ ነገሩ ውስጥ ከጠቀሳቸው ስሞች አንዱ ለዚህ ሐረግ ባለቤት የሆነ መስሎት ይሆናል ። አለዚያም መላልሶ ቢያነበው በቀላሉ ሊያስወግደው የሚችለውን አንድ የማያስፈልግ ነገር ጨምሯል ። ለምሳሌ ፡ “ሰውነታችን በሽተኛ በመሆኑ” ከሚለው ውስጥ መሆኑ በሚለው ላይ የወደቀውን “በ”ን እንደሌለ ቆጥሮት ሊሆን ይችላል ። እንዲህም ሲሆን በሐሳቡ “የሰውነታችን በሽተኛ መሆን” የሚለው ለዚያ ለተጠቀሰው ሐረግ ባለቤት የሆነ መስሎት ይሆናል ። በርግጥ እንዲህ ቢለው ኖሮ ዐረፍተ ነገሩ ከፊተኛው ሁኔታው ትንሽ የተሻለ ይሆን ነበር ።

ም. 91 በከተማው ውስጥ የምንኖረው የተጣራ አየር ባለማግኘት የሰውነታችን በሽተኛ መሆን በየስፍራው ሆስፒታሎች

እንዲቋቋም አድርጓል ።

ቢል ኖሮ ማለታችን ነው ። ነገር ግን ፡ አሁንም የአሰካክ ጉድለት አለበት ። ማሰሪያ አንቀጹ ግን ባለቤት አግኝቷል ማለት እንችላለን ። ብዙ ለውጥ ሳይደረግበት ዐረፍተ ነገሩን ባለበት ሁናቴ ለማሻሻል ቢፈለግ አንድ ባለቤት የሚሆን ተስማሚ ስም መጨመር ያስፈልጋል ። ለምሳሌ ይህን ተጨማሪ ስም "መንግሥት" ብለን እሱን በማስገባት ዐረ ፍተ ነገሩን እንደሚከተለው ልናቃናው እንችላለን ።

ም. 92 በከተማው ውስጥ የምንኖር ሰዎች በመርዝ ጢስ ታፍነን የተጣራ አየር ባለማግኘታችን ሰውነታችን በሽተኛ በመሆኑ መንግሥት በየስፍራው ሆስፒታሎች እንዲቋቋሙ አድርጓል ።

ይህ ዐረፍተ ነገር ከፊተኛው በጣም የተሻለ ይሆናል ። ነገር ግን ፡ አሁንም እናቃናው ካልን የስዋስው ሳይሆን ያስተሳሰብ ጉድለት አናጣበትም ። የሆነ ሆኖ በስም ሙያ ምክንያት የደረሰው ጉድለት ተቃንቷል ልንል እንችላለን ።

ሦስተኛ መልመጃ

የሚከተሉት ዐረፍት ነገሮች በስም ሙያ ምክንያት የተዛቡ ናቸው ፡ ጉድለታቸውን እያስተካከልክ ጻፋቸው ።

1. በአጋሰስ ወይም በእግር ሩቅ መንገድ ተጉዞ ፡ በበሬ ጉልበት ታርሶ በሚኖርበት ዘመን ባለመፈጠሬ እጅግ አስደስቶኛል ።
2. በዚያ በድንቁርና ዘመን እርሻ እንዳሁኑ ዘመን ባለመሻሻሉ በመሬትም የምታፈራው በቂ ባለመ ሆኑ የችጋርና የመከራ ዘመን ቢባል አያንስውም ።
3. ይህች አገር በቅርቡ በጕሳ ልዩነት ጦርነት ተነሥቶ

ብዙ ሕዝብና ሀብት ጠፍቷል ።

4. ከሁለት ዓመታት በፊት በዘርና በሃይማኖት የተፈጠረው ግጭት ከብዙ ጥፋት በኋላ በዚህ ዓመት ግርግሩ ተፈጽሟል ።
5. የጦርነቱ ምክንያት ኢቦ የተባሉ ጐሳዎች ከፌደራል ናይጀርያ መንግሥት ተነጥለው የግል መንግሥት ለማቋቋም ነበር ።
6. ለመገንጠል የሚፈልጉት ሰዎች የናይጀሪያ ጦርነት ጥሩ ምሳሌ ሊሆን ይችላል ።
7. በዚያን ጊዜ ያበሳጨኝ እሳቸው ልብሱን ሁሉ በመመኘታቸው ነው ።

# ምዕራፍ ሁለት

2· ቁጥር

በአማርኛ ሁለት ቁጥሮች አሉ ፡ እነሱም ነጠላ ቁጥርና ብዙ ቁጥር የሚባሉት ናቸው ። ነጠላ ቁጥር የሚያመለክተው አንድ ስም በዐይነቱ አንድ ብቻ መሆኑን ነው ። ለምሳሌ ፡ ሁለት ፡ ሦስት ወዘተ· ያልሆነ ማለታችን ነው ።

አጅ ፈረስ—ሰው—ወረቀት—

ብዕር—መጽሐፍ—በር—ላም—ኮት— ወዘተ···

የብዙ ቁጥር የሚሳየው አንድ ዐይነት ነገር ብዛቱ ከአንድ በላይ መሆኑን ነው ። በአማርኛ አንድ ስም በብዙ መነገሩን የምናውቀው "ኦች" የሚለው ባዕድ መድረሻ ወድቆበት ስናገኝ ነው ።

አጅ እላይ የጠቀስናቸው ነጠላ ስሞች ፡ ወደ ብዙ ቁጥር ሲለወጡ እንደሚከተለው ይሆናሉ ።

ፈረስ — ፈረሶች — ሰው — ሰዎች

ወረቀት — ወረቀቶች — ብዕር — ብዕሮች

መጽሐፍ — መጽሐፎች — በር — በሮች

ላም — ላሞች — ኮት ኮቶች

ነገር ግን ፡ ኦች የሚለው የማባዣ ምልክት መድረሻ ቸው (መጨረሻ ፊደላቸው) ሳድስ ካልሆኑ ስሞች ጋር ሲገናኝ "ዎች" ይሆናል ።

አድ

ክፉ ......................................ክፉዎች

ጠረጴዛ ................................ጠረጴዛዎች

ተራራ .................................ተራራዎች

ተማሪ .................................ተማሪዎች

ከበሮ ....................................ከበሮዎች

በሬ .......................................በሬዎች

ፍሬ ............................ፍሬዎች ወዘተ.

2·1 ስለ ቁጥር የተለያዩ አስተያየቶች

እላይ በተጠቀሰው መሠረት ነጠላን ስም ወደ ብዙ ቁጥር መለወጫው ዘዴ ቀላልና ምቹ ይመስላል ። ነገር ግን ፡ አንዳንድ የሰዋስው ደራሲዎች በሐሳብ ጥቂት ይለያያሉ ። አንዱ ወገን ለስሞች ሁሉ "ኦች" የሚለውን የማብዣ ምልክት ይመርጣል ። በዚህ መንገድ የሔድን እንደሆን አንዳንድ ስሞች ሲበዙ ለጆሮአችን እንግዳ የሚሆኑ ቃላት ያጋጥሙናል ።

አድ "ቦታ" የሚለውን ቃል እላይ በተጠቀሰው ፀዋጅ መሠረት ብናበዛ "ቦቶች" እንዲሁም ፍሬ—ፍሮች እንጀራ—ብሎ እንጀሮች ሊል ነው ።

ከዚህም በላይ ይህን ዘዴ የተቀበልን እንደሆን አንዳ ንድ በትርጉም የሚለያዩ ስሞች በብዙ ቁጥራቸው ላይ አንድ ሊሆኑና ሊያደናግሩ ነው ።

አድ "ሥር" የሚለውና "ሥራ"የሚለው ቃል የብዙ ቁጥር ሥሮች ሊሆን ነው ። እንዲሁም ስፍራና ስፍር ስፍሮች ወሬና ወር ወሮች መባላቸው ነው ።

በብላታ መርስዔ ሐዘን "ያማርኛ ሰዋስው" ውስጥ በገጽ 33

በ1948 ዓ ም በወጣው በአራተኛው እትም እንዲህ የሚሉ ሦስት ዐይነት ዐዋጆች እናገኛለን ።

ሀ  መድረሻው ራብዕ ፡ ሳድስ የሆነ ቃል የመጨረሻ ፊደሉን ሳብዕ አድርጎ "ች" ይጨመርበትና ብዙ ይሆናል።

ምሳሌ ጌታ — ጌቶች ሰው — ሰዎች እንደ ማለት ነው ።

ለ  መድረሻው ሳብዕ የሆነ ቃል የመጨረሻ ፊደሉ ሳይለወጥ "ች" ይጨመርበትና ብዙ ይሆናል ።

ምሳሌ በቅሎ— በቅሎች ፡ መሰንቆ —መሰንቆች እንደ ማለት ነው ።

ሐ  መድረሻው ካብዕ ፡ ሣልስ ፡ ሃምስ የሆነ ቃል መጨረሻ ፊደሉ ሳይለወጥ "ዎች" ይጨመርበትና ብዙ ይሆናል ።

ምሳሌ ፡ ክፉ....ክፉዎች ፡ ፊታውራሪ....ፊታውራሪዎች ፡ ገበሬ ....ገበሬዎች ።

በቅድሙ ዐዋጅ መሠረት ቅር እንደ ተሰኘን ሁሉ ፡ በዚህም ዐዋጅ የዚያኑ ዐይነት ችግር ይገጥመናል ።

ምሳሌ ፡ በራብዕና በሳድስ የሚደርሱትን ሁሉ መድረሻቸውን ሳብዕ እያደረግን "ች" ከጨመርንቦታ የሚለውን ቦቶች ፡ ሥፍራ....የሚለውን ሥፍሮች ፡ ሥፍር....የሚለውንም ሥፍሮች ሥር....የሚለውንም ሥሮች ልንል ነው ።

በሳብዕ የሚደርሱትም እንዲሁ ምንም ሳይለወጡ "ች" ከተጨመረባቸው ዳቦ....ዳቦች ፡ ፋኖ....ፋኖች ፡ መሮ...

መሮች ፡ ዐሦ....ዐሦች ፡ሊ.ያስኝ ነው ።

ስለዚህ ፡ እላይ በተጠቀሰው ደራሲ ውሳኔ መሠረት የሔድን እንደሆነ ያለመድናቸውን ቋንቋው የማይፈቅደውን ዐይነት ያበዛዝ ሕግ ለማስለመድ እንደ መሞከር ይቆጠራል ። ከዚህ ሁሉ ችግር ለመዳን ቀላሉ መንገድ እላይ እንደ ጠቀስነው ሁሉ በሳድስ የሚደርሱትን መጨረሻቸውን ሳብዕ አድርጎ "ች" መጨመር ። ለቀሩት ግን በሙሉ "ዎች" የሚለውን ቅጥያ ያለ ምንም ለውጥ መጨመር የተሻለ መንገድ ነው ። ብላታ መርስዔ ሐዘንም ይህንኑ እንዶ ተው በተጠቀሰው በገጽ 33 "ይህ ውሳኔ በአንድ ዓይነት ደምብ የተደነገገ ስለሆነ ለሕሊና የሚስማማ ነው" በማለት የደገፉት ይመስላሉ ።

2·2 የግዕዝ ስሞች አበዛዝ

አንድ ነጠላ ስም ወደ ብዙ የሚለወጠው ፡ አሁን በተጠቀሰው ሥርዓት ማለት "ኦች"ንና "ዎችን" በማስገባት ብቻ አይደለም ። ባማርኛ ቋንቋ ውስጥ ከግዕዝ ቋንቋ የተወረሱ ብዙ ስሞች አሉ ። እነዚህም ስሞች በአማርኛ ሥነ ጽሑፍም ሆነ በንግግር እየገቡ በሰፊው ይሠራባቸዋል ። እነሱም አብዛኞቹ የግዕዝን የማባዣት ሥርዓት እንደያዙ ወደ አማርኛ ገብተዋል ። በግዕዝም ቋንቋ የማብዣት ዘዴ ብዙ ዐይነት ስለሆነ ፡ ሁሉንም የሚያጠቃልል አንድ ዐዋጅ መስጠት ያስቸግራል ። በጣም ከተለመዱት ውስጥ ጥቂቶቹን እንመልከት ።

ካህን....ካህናት ፡ ጳጳስ....ጳጳሳት ፡ ቃል.... ቃላት ፡ መነኩሴ....መነኮሳት ፡ ሐዋርያ....ሐዋር

ያት ፡ ንጉሥ ....ነገሥታት ፡ ነገሥት ፡ ነቢይ....ነቢያት ፡

መጽሐፍ....መጻሕፍት ፡ መምህር....መምህ

ራን ፡ መስፈን....መሳፍንት ፡ ደብር....አድባራት ፡

ቄስ....ቀሳውስት ፡ መልአክ....መላእክት ፡ ሊቅ....

ሊቃውንት

ቤት....አብያት ፡ ሀገር....አህጉር ፡ ርእስ....

አርእስት

ሕዝብ....አሕዛብ ፡ ዐምድ....አዕማድ ፡ ገዳም

...ገዳማት

አንቀጽ....አናቅጽ ድንግል....ደናግል

አንበሳ....አናብስት

ተዋናይ....ተዋናያን ማኅበር .... ማኅበራት

ኢትዮጵያ....ኢትዮጵያውያን

ብዙ የግዕዝ ስሞች የብዙ ቁጥር መሆናቸውን ባለመገንዘብ በአማርኛ ደምብ "ኦች" እየተጨመረባቸው የብዙ ብዙ እየሆኑ ሲነገሩና ሲጻፉ ይገኛሉ ። ይህ ዘዴ በራዲዮ ፡ በጋዜጣና እንዲሁም ባንዳንድ መጻሕፍት ውስጥ እንደሚሠራበት የተረጋገጠ ነው ። ይሁንና ይህን ስሕተት ባማርኛ እንዲለመድ ያደረጉና አሁንም በየጊዜው ይህንኑ የሚደጋግሙ የግዕዝ ቋንቋ ዕውቀት የሌላቸው ሰዎች ናቸው ።

አይ ቃልና/ቃላት በነዚህ ሰዎች የቃላት አስተሳሰብ የነጠላ ቁጥር ስሞች ናቸው ። እንዲሁም መጽሐፍና መጻሕፍት ፡ መምህርና/መምህራን ፡ ጳጳስና/ጳጳሳት ፡ ሐዋርያና/ሐዋርያት ሌሎችም አያሌ ቃላት በነዚሁ ሰዎች ዘንድ እንደ ነጠላ ስለሚቆጠሩ ፡ እንደገና የአማርኛውን ማብዣ "ዎች"ን

እየጨመሩ በግዕዝ የበዛውን ስም እንደሚከተለው ያበዙ ታል።

ቃላት.....ቃላቶች .... መጻሕፍት .... መጻሕፍቶች
መምህራን .... መምህራኖች ፡ ጳጳሳት .... ጳጳሳቶች
ሐዋርያት .... ሐዋርያቶች ፡
አርእስት .... አርእስቶች* እንደ ማለት ነው ።

የዚህ ዐይነቱ ስሕተት በተማሪዎች ድርሰት ውስጥ በሰፊው ይገኛል ።

<u>ለምሳሌ</u> ፡ ይህን ቃላት አላውቀውም የሚል ተማሪ "ቃላት"ን እንደ ነጠላ ስም መቁጠሩ ግልጽ ነው ። ይኸውም ተማሪ ስለሁለት ወይንም ከዚያ ስለሚበልጡ ቃላት ለመናገር ቢፈልግ ኑሮ እነዚህን ቃላቶች አላውቃቸውም እንደሚል አያጠራጥርም ።

ስለዚህ ከእንደዚህ ያለው ስሕተት ለመዳን ማንኛውም ተማሪ የግዕዙን የማብዛት መንገድ ደኅና አድርጎ ማወቅ አለበት ።

አሁን ያየነው ዐረፍተ ነገር ማለት "ይህን ቃላት አላውቀውም" የሚለው ሲቃና "እኒህን ቃላት አላውቃቸ ውም" አለዚያም በነጠላ ለመናገር "ይህን ቃል አላውቀ ውም" መባል አለበት ። የግዕዙን ቃል በግዕዙ ሥርዓት ማብዛት የተመረጠ ያጸጻፍ መንገድ ነው ። የግዕዝ ቃላት በአማርኛ ሥነ ጽሑፍ ውስጥ እየገቡ ለጽሑፉ ወዝና ለዛ

---

* ምንም እንኳ በግዕዝ የአርእስት ነጠላ "ርእስ" የሚለው ቃል ቢሆንም ባማርኛ ይህ ቃል (ርእስ) ስላልተለመደ "አርእስት" የሚለውን እንደ ነጠላ ቆጥረን ስናበዛው "አርእስቶች" ማለት ይኖርብናል ።

ሲሰጡት ፡ የስሚንም ጆሮ ይማርካሉ ። ይሁንና የግዕዙን የብዙ ቁጥር ያላወቀ በአማርኛ ሥርዓት ነጠላውን ቃል ወደ ብዙ ቢለውጥ ፡ ሰሚን አያስደስት እንጂ ሰዋስዋዊ ጉድለት አደረገ አይባልም ። ይህም ፡

ቃል.....ቃሎች ፡ መምህር .... መምህሮች

ሊቅ ....ሊቆች ፡ መጽሐፍ .... መጽሐፎች እንደማለት ነው ።

ከዚህ ቀጥለን የአ፡ንገ ቅጽል ስለሚከተላቸው ስሞች ያበዛዝ ሥርዓት እንነጋገር ።

2.3 በዐረፍተ ነገር ውስጥ የስምና የግሥ በቁጥር መስማማት

2·3·1 አንዳንድ የቋንቋ መምህራን ስሞች በሚከተላቸው የአ፡ንገ ቅጽል መሠረት ነጠላ ወይንም ብዙ መሆን አለባቸው ይላሉ ። ይህም አንድ ፈረስ ፡ ሁለት ፈረሶች እንደ ማለት ነው ።

እንዲሁም በዐረፍተ ነገር ውስጥ እነዚህ ስሞች በቁጥራቸው መሠረት ከግሣቸው ጋር መስማማት አለባቸው ብለው ያውጃሉ ።

ም·1 አንድ ፈረስ አለኝ ።

ም·2 ሁለት ፈረሶች አሉኝ መባል አለበት ይላሉ ።

ይህ ዐዋጅ አያሌ ተማሪዎችን ያዳናግራል ፡ መምህሩ "ሁለት ፈረሶች" እንጂ "ሁለት ፈረስ" ማለት የለብህም ሲለው ፡ ከክፍል ውጭ ደግሞ በብዛት የሚሰማው "አንድ ፈረስ" ሁለት ፈረስ ፡" ወይም "ዐሥር ፈረስ" የሚለውን አነጋገር ነው ። ይሁንና እኛ መከተል ያለብን አብዛኛው ተናጋሪ የሚለውን ነው ። ይህም የሚሆንበት የቋንቋ ሕግ

የሚወጣው የቋንቋው ባለቤት የሆነው ሕዝብ የሚናገርበትን መንገድ በመከተል ስለሆነ ነው ። ስለዚህ "ሁለት ፈረስ" ፡ "ሦስት ፈረስ" ማለት ቋንቋው የሚፈቅደው ሕግ ነው ለማለት ይቻላል ።

እንዲሁም ስሙ በቁጥር ከግሡ ጋር መስማማት አለበት የሚለውንና ፡ ስሞች በእነዛቸው መጠን ብዙ ወይንም ነጠላ ይሁኑ የሚለውን ዐዋጅ በማጣመር ዐረፍተ ነገሮች ሠርተን ብንመረምር ለጆሮ እንግዳ የሚሆን አነጋገር ይገጥመናል ።

ም·3 ዐሥር ብሮች አሉኝ ።

ም·4 ለተጣራው ጠጅ ሦስት ጋኖች ያስፈልጋሉ ።

ም·5 ሦስት ሳምንቶች ካለፉ በኋላ መጣሁ ።

ም·6 ዐሥራ ሁለት ወሮች አንድ ዓመት ይሆናሉ ።

ም·7 ዕድሜዬ ሐያ ስድስት ዓመቶች ናቸው ።

እነዚህ ዐረፍተ ነገሮች በተለመደው አነጋገር እንደሚከተለው ይሆናሉ ።

ም·8 ዐሥር ብር አለኝ ።

ም·9 ለተጣራው ጠጅ ሦስት ጋን ያስፈልጋል ።

ም· 10 ሦስት ሳምንት ካለፈ በኋላ መጣሁ ።

ም· 11 ዐሥራ ሁለት ወር አንድ ዓመት ይሆናል ።

ም·12 ዕድሜዬ ሐያ ስድስት ዓመት ነው ።

ስሞች ከእነዝ ቁጥራቸው ከግሥ ጋር መስማማት አለባቸው የሚለው ዐዋጅ የሚጸናበት ጊዜ በሚከተለው ሁናቴ ብቻ ነው።

1· አስፈላጊ ሆኖ ስሙ በብዙ ቁጥር ከተነገረ ፡ ስለሱ የሚናገረውም ግሥ የብዙ ቁጥር መሆን አለበት ።

ም· 13 ሦስት ሰዎች መጡ እንጂ

ሦስት ሰዎች መጣ አይባልም ።

ግን ቀድመን እንደ ጠቀስነው ፡ ሰው የሚለው ቃል ሳይበዛ ከተነገረ ምንም እንኳ ተከታዩ አኃዙ ብዙነት ቢያመለክትም ግሡ ነጠላ መሆን አለበት ። ይኸውም ፡

ም·14 "ሦስት ሰው መጣ" እንደ ማለት ነው ።

2· ስሙን ቀድሞ የሚነገረው አኃዝ ካንድ የበለጠ ሆኖ መስተአምር ሲኖረው ስሙ ይበዛል ። ግሡም በዚያው መሠረት የብዙ ቁጥር መሆኑ ግልጽ ነው ።

ም·15 ሦስቱ ተማሮች ዛሬ አልመጡም ።

ም·16 አምስቱ መጻሕፍት ዛሬ ተሸጡ ።

2·3·2 አንዳንድ ሰዎች "ክፉዎች ልጆች" የሚለውን መንገድ ሲመርጡ ብዙዎች ግን "ክፉ ልጆች" የሚለውን መንገድ ይከተላሉ ። የቋንቋ ሕግ ሁለተኛውን መንገድ የሚደግፈው ይመስላል ። ይህም ማለት በብዙ ቁጥር የተነገረውን ስም የሚገልጽ ቅጽል በነጠላው ቢነገር ባማርኛ እንደ ጸያፍ አይቆጠርም ማለት ነው ።

ም·17 ጥሩ መምህራን ናቸው ።

ም·18 ጠንካራ ገበሬዎች አይደሉም ።

ም·19 እንደነሱ ስስታም ሴቶች አላየሁም ።

ም· 20 በዚህ ክፍል ብዙ ጨዋ ተማሮች አሉ ።

2·3·3 ነገር ግን ቅጽሉ መስተአምር ሲኖረውና ስሙ የብዙ ቁጥር ቢሆን ቅጽሉ የግድ መብዛት አለበት ። እንዲሁም ማለት "ጥቁሩ ሰው" የሚለውን ስናበዛ ፡ "ጥቁሮቹ ሰዎች" እንላለን ማለት ነው ። "ጥቁር ሰዎች" እንዳልን

ሁሉ "ጥቁሩ ሰዎች" ማለት አንችልም ።

2·3·4 አንዳንድ ቅጽሎች የተለየ የራሳቸው የማብዛት ሥርዓት አላቸው ። እነዚህም ቅጽሎች የሚከተሉት ዐይነት ናቸው ።

ደግ — ደጋግ ፡ ጥቁር — ጥቋቁር

ረጅም — ረጃጅም ፡ ትልቅ — ትልልቅ (ትላልቅ)

ትንሽ — ትንንሽ (ትናንሽ) አጭር — አጫጭር

ቀይ — ቀያይ ፡ ነጭ — ነጫጭ ወዘተ ...

እንደነዚህ ያሉት የብዙ ቁጥር ቅጽሎች የሚገልጿቸው ስሞች አብዛኛውን ጊዜ በብዙ ቁጥር ይነገራሉ ። ይሁንና አንዳንድ ጊዜ በነጠላ ቢነገሩ አባባሉ እንደ ጸያፍ አይቆጠርም ።

ትልልቅ ዛፎች — ትላልቅ ዛፍ

ቀያይ ዶሮች — ቀያይ ዶሮ

ጥቋቁር ፍየሎች — ጥቋቁር ፍየል — አጫጭር ዛፍ

## አምስተኛ መልመጃ

ለሚከተሉት የግዕዝ ስሞች የብዙ ቁጥር ስጥ ፡

ደራሲ — ጸሐፊ — መጋቢ — አምላክ —

ባሕርይ — እንስሳ — ዕፅ — መልአክ — ዘመን —

ዓመት — ዕለት — ልብስ

ዐቢይ — መሃይምን — ዓለም — ኮከብ — ምሁር —

ድንግል — ሐዋሪ — መንፈስ

ሕዋስ — ድኩም — ዕውር — ሕሙም —

ቅድስት — ሰይጣን — ጥንታዊ —

## ስድስተኛ መልመጃ

ከዚህ ቀጥለው የተጻፉት በቁጥር ረገድ የተዛቡ ዐረፍተ ነገሮች ናቸው ። እያቃናህ ጻፍ ።

1· የዘመኑ ወጣት ጊዜ ማሳለፊያ እጅግ በርካታ ናቸው ።

2· የሆነው ሆኖ የዓለም ሕዝብ ተባብሮ የወንድማማችነት መንፈስ እስኪያድርበት ድረስ እነዚሁ ችግሮች ምን ጊዜም ሲያንገላቱት ኖሯል ።

3· የጠፈር ዐዋቂዎች ማርስን ለመጀመሪያ ለመመርመር የፈለጉበት ምክንያቶች ብዙ ናቸው ።

4· የሰው ልጅ የሚያደርገው የጠፈር ጉዞዎች በሥነ ፍጥረት በኩል ጠቃሚ መሆናቸው የማይጠረጠር ነው ።

5· ለዘመኑ ወጣቶች ብዙ የጊዜ ማሳለፊያዎች ሥፍራ አለ። ከነዚሁም መካከል ደግን ነገር ብቻ የተከተለ ሳይሆን ጥፋትን የሚያስከትልና መሠረታዊ ባህልም የለቀቁ አካባቢዎች ይገኙበታል ።

6· ባሁኑ ዘመን ለወጣቶች ከሚያስፈልጉት ነገሮች አንዱ የዕረፍት ጊዜ ማሳለፊያ ቦታዎች ነው ።

7· የዘመኑ ወጣት ትምህርት የሚቀስምበትና በጥሩ ሞራል የሚያድግበት ሥፍራዎች ሲኖሩ በሌላው በኩል ደግሞ ከባህል ውጭ የሆኑ ጠባዮችንና አስተሳሰቦችን የሚገበይበት የጊዜ ማሳለፊያ ሥፍራዎች አሉ ።

8· የዘመኑ ወጣት ጊዜውን የሚያሳልፍባቸው ቦታዎች ቁጥራቸው በርከት ያሉ ናቸው ።

9· ድር አንድምናውቃቸው በጣም ቀጪን ክር ነው ።

እንኳን እንደ ሰውና እንደ እንስሳ ያለው ኃይለኞች ነገሮች ነክተውትና ነፋስ ቢነፍስበት እንኳ ቶሎ የሚበጠስ ነገር ነው።

10· የቃላት አለቦታቸው መግባት ትርጉም ስለሚለውጡ በጣም መጠንቀቅ ያስፈልጋል ።

11· ብዙ ቃላቶች ማወቅ ድርሰት ለመጻፍ ይረዳሉ ።

# ምዕራፍ ሦስት

3· ጾታ

አንዳንድ የሰዋስው ደራሲያን ጾታን በአራት መደብ ይመድቡታል ። አመዳደባቸውም ተባዕታይ ፡ አንስታይ ፡ ግዑዝና የወል በማለት ነው።

| ግዑዝ | የወል | ተባዕታይ | አንስታይ |
|---|---|---|---|
| ድንጊያ | ሐኪም | አባት | እናት |
| ጠረጴዛ | አስተማሪ | ወንድም | እኅት |
| እርሳስ | ጸሐፊ | በሬ | ላም |
| ወንበር | ልጅ | አበበ | አበበች |
| እንጀራ | ተማሪ | ወንድ | ሴት |

ለምሳሌ ያህል የሚከተሉትን ዐረፍተ ነገሮች እንመልከት ።

ም· 1 ከበደ እዚህ ነው ።

ም· 2 ዘነበች እዚህ ናት ።

አሁን በተጠቀሱት ምሳሌዎች ለተባዕታይና ለአንስታይ ስሞች የገባው የመሆን ግሥ ሁለት መልክ ይዞ እናያለን ። "ከበደ" ለሚለው ተባዕታይ ስም "ነው" የሚለው "ዘነበች" ለሚለው አንስታይ ስም "ናት" የሚለው ገብቷል ።

በዚህ መንገድ የቀሩትን ሁለቱን ማለት ግዑዝና የወል

ዖታዎች ስንመለከት እላይ ከተጠቀሱት የሚለዩበት መንገድ ፈጽሞ አይገኝም ። ምክንያቱም በዐረፍተ ነገር ስናስገባቸው የሚያሳዩት ጠባይ ወንድነትን ወይንም ሴትነትን ስለሚሆን ነው ።

ም· 3 ድንጋይ ከባድ ነው ።

ም· 4 ሐኪም ፈዋሽ ነው ።

እዚህ ላይ ድንጋይ የተባለው ግዑዝ ስምና ሐኪም የተባለው የወል ስም በተባዕታይ ዖታ እንደገቡ አስተውል ።

በእነዚህ ስሞች ላይ የተወሰነውን አመልካች "ዋ"ን ብንጨ ምር በአንስታይነት እንደሚያገለግሉ ማድረግ ይቻላል ።

ም· 5 ድንጋይዋ ከባድ ናት

ም· 6 ሐኪሟ ጉበዝ ናት

ስለዚህ ግዑዝና የወል የተባለው አከፋፈል ምንም አገልግ ሎት እንደሌለው መረዳት ይቻላል ። እንግዲህ በአማርኛ ያሉን የዖታ ዐይነቶች ተባዕታይና አንስታይ ብቻ መሆናቸው ነው ።

ነገር ግን ፡ በአማርኛ ስሞች በብዙ በተነገሩ ጊዜ ግሡ የተባዕታይንም ሆነ የአንስታይን ጠባይ አያመለክትም ።

ም· 7 እነ ከበደ እዚህ ናቸው ።

ም· 8 እነዘነበች እዚህ ናቸው ።

ም· 9 ከበደና ዘነበች እዚህ ናቸው ።

ም· 10 ሐኪሞች እዚህ ናቸው ።

ም· 11 ድንጊያዎች እዚህ ናቸው ።

እላይ እንዳየነው ፡ ለተባዕታይም ሆነ ለአንስታይ የገባው ግሥ "ናቸው" የሚለው ቃል ነው ።

በድጋሚ ለማስታወስ ያህል ፡ ስሞች በዐረፍተ ነገር ውስጥ በገቡ ጊዜ ከግሡ ጋር በዖታ መስማማት አለባቸው ። ይኸውም ተባዕታይ ስም በነጠላ ከተነገረ ፡ ተባዕታይ ግሥ እንዲሁም

አንስታይ ስም በነጠላ ከተነገረ አንስታይ ግሥ ያስፈልገዋል ማለት ነው ።

ም· 12 ከበደ መጣ እንጂ
ከበደ መጣች አንልም ።
እንዲሁም

ም·13 ዘነበች መጣ አንልም ።

ነገር ግን ፡ አንዳንድ ጊዜ ወንድን በሴት ግሥ ፡ ሴትን ደግሞ በወንድ ግሥ መጥራት የተለመደ ነው ።

ምሳሌ ፡

ም· 14 ከበደ መጣች

ም· 15 ከቤ መጣች

በዚህ መንገድ የሚናገሩ ሰዎች በዕድሜና በወዳጅነት በጣም የሚቀራረቡ ሲሆኑ ለመግለጽ የሚፈለገውም ቁልምጫ ነው ።

እንዲሁም አንዱን ተባዕታይ የሆነ ስም ለማሳነስ ወይንም ለማኮሰስ በተፈለገ ጊዜ በአንስታይ ግሥ ይነገራል ።

ምሳሌ ፡

ም· 16 ጠረጴዛይቱ ታምራለች

ም· 17 በቀለ ! አሁን አንቺ ወንድ ሆንሽ!

3·1 <u>በዐረፍተ ነገር ውስጥ የፆታ አለመስማማት የሚያስከትለው ሰዋስዋዊ ጉድለት</u> ከላይ በተገለጸው መሠረት የሚከተሉት ዐረፍተ ነገሮች ምን ዐይነት የፆታ ጉድለት እንዳለባቸው እንመርምር ። .

ም ·18 ከቤታችን በላይ ያለችው የወይራ ዛፍ ቅርንጫፎች የተስተካከሉና ክብብ ያሉ ስለሆኑ ፡ ከሩቅ ሲታይ አነስተኛ ጎጆ ትመስላለች ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ <u>የወይራ ዛፍ</u> ለሚለው ስም እንደ

ገላጭ ሆኖ የገባው "ከቤታችን በላይ ያለችው" የሚለው ሐረግ ነው ። ያለችው የሚለውን ቃል ለብቻው ነጥለን ያስተዋልን እንደሆን የሚመለክተው አንስታይ ፆታን ነው ። በዚህም አኳኋን የሚገለጸው ዋናው ስም ማለት "ዛፍ" የሚለው ቃል ፆታው አንስታይ ሆኗል ። ስለዚህ ስለሱ የሚነገረውም ማሰሪያ ግሥ አንስታይ መሆን ስላለበት "ትመስላለች" የሚለው ቃል አንስታይ መሆኑ ተገቢ ነው ።

ነገር ግን ፣ እማሰሪያው ግሥ ስንደርስ "በዛፍ" ና በትመስላለች መካከል የሚገኙትን የፆታ መለያ ምልክት የሚገኝባቸውን ቃላት የመረመርን እንደሆነ ፆታቸው ተዛብቶ እናገኛለን ። "ቅርንጫፎቹ" በሚለው ቃል ውስጥ የቃሉ መድረሻ "ካእቡ" "ቹ" የሚያመለክተው ተባዕታይ ፆታን ነው ። በዚህ ምክንያት ፣ "ከቤታችን በላይ ያለችው" ከሚለው ከ"ዛፍ" ገላጭ ጋር በፆታ አልተመሳሰሉም ማለት ነው ። ስለዚህ ፆታቸውን ለማስተካከል የተፈለገ እንደሆነ ሁለት መንገድ አለን ። 1ኛ/ የዛፍን ፆታ ተባዕታይ ማድረግና ገላጩን ተባዕታይ ማድረግ "ያለችው" በማለት ፈንታ "ያለው" ብሎ ማንበብ ። ማለት "ከቤታችን በላይ ያለው የወይራ ዛፍ ቅርንጫፎቹ" ብለን መሔድ ። አለዚያም የዛፍን ፆታ እንደ ዐረፍተ ነገሩ አጀማመር በአንስታይ ትቶ ቅርንጫፎቹ በማለት ፈንታ "ቅርንጫፎቿ" ብሎ ማስተካከልና "ከቤታችን በላይ ያለችው የወይራ ዛፍ ቅርንጫፎቿ" ብሎ ማንበብ ። በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ያለው ስሕተት ይህ ብቻ አይደለም ። "ከሩቅ ሲታይ" የሚለውም ሐረግ ከሌሎች ሐረጎች ጋር በፆታ አልተስማማም ። "ሲታይ" የሚለው ቃል የሚናገረው ስለ ተባዕታይ ፆታ ነው ። ስለዚህ "ሲታይ

አንስተኛ ጐጆ ትመስላለች” የሚለው አነጋገር የተዛባ ነው ። ይህንንም ለማስተካከል “ቅርንጫፎቹ” ስለሚለው ቃል በተናገርነው መሠረት የዛፍን ፆታ ተባዕት ያደረግን እንደሆን ሌሎቹንም ወደ ተባዕታይነት መለወጥ ፤ አለዚያም በአንስታይነቱ ከቀረ ፤ “ሲታይ” በማለት ፈንታ “ስትታይ” ማለት ይኖርብናል ። በዚህ ሁናቴ የተስተካከለው ዐረፍተ ነገር በሁለቱም መንገድ እንደሚከተለው ይሆናል ።

ም· 19 የዛፍ ፆታ ተባዕታይ ሲሆን ፤ ዐረፍተ ነገሩ የሚቀጥለውን መልክ ይይዛል ።

ከቤታችን በላይ ያለው የወይራ ዛፍ ቅርንጫፎቹ የተስተካከሉና ክብብ ያሉ ስለሆኑ ፤ ከሩቅ ሲታይ አንስተኛ ጐጆ ይመስላል ።

ም· 20 የዛፍ ፆታ አንስታይ ሲሆን ዐረፍተ ነገሩ እንደሚከተለው ይነበባል ።

ከቤታችን በላይ ያለችው የወይራ ዛፍ ቅርንጫፎቿ የተስተካከሉና ክብብ ያሉ ስለሆኑ ፤ ከሩቅ ስትታይ አንስተኛ ጐጆ ትመስላለች ።

ሌላ ዐረፍተ ነገር ደግሞ እንመርምር ።

ም· 21 ቅድም ያቀረብኩትም ጥያቄ ይህንኑ ጉዳይ የተመረኰዘች ስለሆነ ፤ በስፊው ልትተችበት ትችላለህ ።

ይህን ዐረፍተ ነገር እንደ ጀመሩ ለመጨረስ የፈለግን እንደሆነ ሁለት ነገር መለወጥ ይኖርብናል ። እነዚሁም “ስለሆነ” እና “ልትተችበት” የሚሉት ቃላት ናቸው ። “ስለሆነ” በማለት ፈንታ “ስለሆነች” ፤ “ልትተችበት” በማለት ፈንታ “ልትተችባት” ብለን ያነበብን እንደሆነ ዐረፍተ ነገሩ በፆታ የተስተካከለ ይሆናል ማለት ነው ።

እንዳለፈው ዐረፍተ ነገር ሁሉ ይህኛውንም በሁለት መንገድ ማስተካከል ይቻላል ።

ም· 22 ቅድም ያቀረብኳትም ጥያቄ ይህንኑ ጉዳይ የተመረኮዘች ስለሆነች በሰፊው ልትተችባት ትችላለህ ።

ም· 23 ቅድም ያቀረብኩትም ጥያቄ ይህንኑ ጉዳይ የተመረኮዘ ስለሆነ በሰፊው ልትተችበት ትችላለህ ።

## ሰባተኛ መልመጃ

ከዚህ ቀጥሎ በዖታ አለመስማማት የተነሣ የተዛቡ ዐረፍተ ነገሮች አሉ ፡ አቃና ።

1/ አቶ ፍሥሐ ገንዘብ የቸገረው ይመስለኛል ፡ እኔ ትንሽ ስላለችኝ ከሱው ላካፍለው እችላለሁ ።

2/ በጨለማ የሚጓዝ ሰው አንዲት ትንሽ ቅጠል ከዛፍ ላይ ስትወድቅ በሚያሰማው ኮሽታ ብዙ ሊደነግጥ ይችላል ።

3/ በመንገዳችን ያገኘናት ወንዝ ጊዜው በጋ ስለነበረ አንዳችም ውሃ አልነበረበትም ።

4/ ስለ አንዲት መጽሐፍ ጥሩነት ከብዙ ሰዎች ስለ ሰማሁ ፡ መጽሐፏን ገዝቼ በጀርባዩ እዛፍ ሥር ተጋድሜ ሳነብ እንዳጋጣሚ የመጽሐፉ ደራሲ ባጠገቤ ሲያልፍ አይቼ በእውነትም የሚደነቅ መጽሐፍ መድረሳቸውን ገለጽኩላቸው ።

5/ በጥርጣሬና በጭቅጭቅ ከኖሩበት ረጅም ዕድሜና ክብር ይልቅ በመዝናናት የኖሩባት አጭር ጊዜና ፡ በአጭሩ ጊዜ ውስጥ የሠሩት መልካም ሥራ ታላቅ ደስታን ይሰጣል ።

# ምዕራፍ አራት

## የሐረግ ዝምድና

### 4 የሐረግ አለመዛመድ

የስምን ሙያ ጠንቅቆ ባለማወቅ ዐረፍተ ነገሮች ሊዛቡ እንደሚችሉ በልዩ ልዩ ምሳሌዎች ተገንዝበ ናል ። ይሁንና ዐረፍተ ነገር የሚበላሸው የስምን ሙያ አገባብ ባለመጠንቀቅ ብቻ አይደለም ። ሌሎችም ብዙ ዐይነት የአስካክ ጉድለቶች አሉ ። ብዙዎች ስሕተቶች የሐረግ አለመዛመድ በሚል ሥያሜ ሊጠቃለሉ ይች ላሉ ። ይኸው የስምን ሙያ ባለማወቅ የሚደረጉትንም ስሕተቶች ይጨምራል ። ስለዚህ በዚህ ምዕራፍ በልዩ ልዩ ምሳሌዎች አማካይነት የሐረጎች ዝምድና እንዴት እንደሚፋለስ እናመለክታለን ።

### 4.1 በወደረኛ መስተፃምር ስለሚያያዙ ሐረጎች

ሐረጎች በዐረፍተ ነገር ውስጥ በብዙ ምክንያቶች ላይዛመዱ ይችላሉ ። በአጭሩ ለመናገር የተፈለገ እንደ ሆን የሐረጎች አለመዛመድ ማለት የዐረፍተ ነገር አለመሳካት ማለት ነው ። ጐላ ያሉትን የሐረጎች አለመዛመድ ለመጥቀስ ያህል በመጀመሪያ በወደረኛ መስተፃምር ስለሚያያዙ ሐረጎች እንነጋገር ። በወደረኛ መስተፃምር በ "ና" የሚጨርሱ ሐረጎች ባወቃቀር

ተመጣጣኝ ወይንም የመስተፃምር ሥያሜ እንደሚያመ ለክተው እቻ መሆን አለባቸው ። ተመጣጣኝም ስንል ስምና ስም ፡ ስምና ተውላጠ ስም ፡ ተውላጠ ስምና ተውላጠ ስም ፡ ቅጽልና ቅጽል ፡ አርእስትና አርእስት ፡ እንዲሁም ጥገኛ ሐረግና ጥገኛ ሐረግ ወዘተ … ማለታችን ነው ። ለምሳሌ አበበና በቀለ ፡ ከበደና አንተ እኔና እርሱ ፡ ክፉና ደግ ፡ መቀመጥና ማጥናት ፡ የማያጠናና የሚያጠና እኒህን የመሳሰሉትን ሁሉ ማለ ታችን ነው ።

ብዙውን ጊዜ ተማሪዎች በዐረፍተ ነገር አስካክ ላይ ስሕተት የሚያደርጉት ጥገኛ ሐረጐችን ተመጣጣኝ ለማድረግ ካለመቻል የተነሣ ነው ። ወደ ዝርዝር ነገር ከመሔዳችን በፊት በጠቅላላ ልንገነዘበው የሚያስፈል ገን ጥገኛ ሐረግ የሚባለው በዘንድ አንቀጽ ላይ ወይንም በማሰሪያ አንቀጹ ላይ ጥገኛ መስተፃምር ወድቆበት የሌላ ዐረፍተ ነገር ማሟያ እንዲሆን የተደረገ ዐረፍተ ነገር መሆኑን ነው ።

ም.1 ከበደ ነገ ይመጣል

የሚለው ራሱን የቻለ ዐረፍተ ነገር ነው ።

እንዲሁም

ም. 2 ከበደ ወንድሜ ነው

የሚለው ራሱን የቻለ ዐረፍተ ነገር ነው ።

እነሆ ሁለቱን ዐረፍተ ነገሮች በጥገኛ መስተፃምር አማካይነት ስናጫፍራቸው እንደሚከተለው ይሆናል ፡

ም. 3 ነገ የሚመጣው ከበደ ወንድሜ ነው

ወይንም

ም. 4 ወንድሜ ነገ የሚመጣው ከበደ ነው

ለማለት ይቻላል ። የመጀመሪያው ዐረፍተ ነገር ፡ የሁለተኛው ዐረፍተ ነገር ክፍል ወይንም ማሟያ ስለ ሆነ፡ እስከ ዛሬ በተለመደው ሥያሜ መሠረት ጥገኛ ሐረግ መሆኑ ነው ። በዚህ ሁናቴ ሁለት ወይም ሦስት ዐረፍተ ነገሮች በወደረኛ መስተፃምር በመያያዝ የአንድ ዐረፍተ ነገር ጥገኛዎች የሚሆኑበት ጊዜ ሞልቷል ።

ም. 5 ይህ ሜዳ በጣም ሰፊ ነው ፡ በመኻሉም ትልቅ ጅረት ያልፋል ፡ ካህናቱ ለጥምቀት ታቦት ይዘው ዳስ ጥለው በዓሉን ያከብሩበታል ።

እነዚህን ሦስት ዐረፍተ ነገሮች በጥገኛና በወደረኛ መስተፃምር በማያያዝ በሚከተለው ሁናቴ አንድ ዐረ ፍተ ነገር ማድረግ ይቻላል ።

ም. 6 ይህ ሜዳ በጣም ሰፊ ስለሆነ ፡ በመኻሉም ትልቅ ጅረት ስለሚያልፍ ፡ ካህናት ለጥምቀት ታቦት ይዘው ዳስ ጥለው በዓሉን ያከብሩበታል ።

እዚህ ላይ በጥገኛ መስተፃምር የተያያዙት ሐረጎች ፡ 1ኛ/ ይህ ሜዳ በጣም ሰፊ ስለሆነ ፡ 2ኛ/ በመኻሉም ትልቅ ጅረት ስለሚያልፍ የሚሉት ናቸው ።

ም. 7 እነዚህ ሁለቱ ሐረጎች ለዋናው ዐረፍተ ነገር ማለት ፡ "ካህናት ለጥምቀት ታቦት ይዘው ዳስ ጥለው በዓሉን ያከብሩበታል" ለሚለው ጥገኛ ሆነዋል ። እንግዲህ ብዙ ተማሪዎች የሚሳሳቱት ሁለቱን ጥገኛ ሐረጎች ተመጣጣኝ እማድረጉ ላይ ነው ። ለምሳሌ የዚህ ዐይነት ሐሳብ ለመግለጥ አንድ የዐሥራ አንደኛ ክፍል ተማሪ የሚከተለውን ዐረፍተ ነገር ጽፏል ።

ም 8 ይህ ሜዳ በጣም ሰፊና በውስጡም ሰው ሠራሽ ጠበል ስለሚገኝበት ፡ ቄሶች ታቦቱን ይዘው በአጠገቡ ዳስ ጥለው ያርፋሉ ።

ተማሪው በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ያጫፈራቸው ሐረጐች "በጣም ሰፊ" "በውስጡ ሰው ሠራሽ ጠበል ስለሚገኝበት" የሚሉትን ነው ። እላይ እንደ ገለጥነው እነዚህ ሐረጐች የማይመጣጠኑ ቅጽላዊና ጥገኛ ሐረጐች ናቸው ። በ"ና" ለማጫፈር የሚቻለው በአወቃቀር የሚመጣጠኑ ሐረጐችን ብቻ ነው ። የዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ ግን ፡ "ይህ ሜዳ በጣም ሰፊ" የሚለው ጥገኛ ያልሆነው ሐረግ የተጫፈረው "በውስጡ ሰው ሠራሽ ጠበል ስለሚገኝበት" ከሚለው ጥገኛ ሐረግ ጋር ነው ። እነሆ እንግዲህ ሁለቱ በወደረኛ መስተፃምር በ"ና" የተጫፈሩት ሐረጐች ባለመመጣጠናቸው ዐረፍተ ነገሩ በሐረጐች አለመዛመድ የተነሣ ተዛብቷል ።

እንደገና ከአንድ መጽሐፍ ውስጥ የተቀዳ ዐረፍተ ነገር እንመርምር ።

ም. 9 እንዲሁም የነበረኝ የሰውነቴ አቀራረፅና ካለኝ ከተፈጥሮ ቁንጅናዬ ጋር ብዙዎቹን ወጣት ወንዶች መማረክ ጀምሮ ኖሮ ፡ በትምህርት ቤት የሚገኙት ወጣቶችና በውጭም ብዙዎች ወንዶች በዐይናቸው ይገርፉኝ ጀመር ።

በዚህ ዐረፍተ ነገር ውስጥ "የሰውነቴ አቀራረፅ" ከሚለው ቀጥሎ ያለው ወደረኛ መስተፃምር "ና" በማጫፈር ረገድ ምንም ሙያ የለውም ። ዐረፍተ ነገሩ ያለ "ና" ቢጻፍ ኖሮ ካለበት ሁናቴ ይሻል ነበር ።

የሰውነቴ አቀራረፅ ካለኝ ከተፈጥሮ ቁንጅና ጋር